# ምዕራፍ ፲

# ሁለተኛው የእንግሊዞች ውል

## በኢትዮጵያ በኩል የተደረገ ዝግጅት፤

ከፋሽስት ቀንበር የኢትዮጵያ ነፃነት ተላቀቀ ከተባለበት እ.ኤ.አ ከግንቦት 5 ቀን 1941 ዓ.ም ጀምሮ፤ የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት በታላቋ ብሪታንያ ወታደራዊ አስተዳደር ተይዞ ምን ያህል እንደተሠቃየ፤ ባለፉት ምዕራፎች ለማስረዳት ተሞክሯል። በተለይ በኢትዮጵያና በታላቋ ብሪታንያ መካከል የተደረገው የመጀመሪያው ውል ከመፈረሙ በፊት፤ ለዘጠኝ ወራት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ሚኒስትሮቻቸውን ሾመው መንግሥታቸውን ለመምራት ሲነሡ፤ ወታደራዊው አስተዳደር አልቀበልም በማለት ያሳየው የዕብሪት መንፈስና የፈጸመው በደል መቸውንም የሚረሳ አይደለም።

እንደሚታወቀው የኢትዮጵያ ነፃነት በተመለሰ ማግሥት፤ በእንግሊዞች ጫና በግዴታ የተፈረመው ውል የሁለት ዓመት ዕድሜ (1942-1944) የተሰጠው ነበር። ነገር ግን ኢትዮጵያ በታላቋ ብሪታንያ ወታደራዊ አስተዳደር የተያዘችው፤ ለሁለት ዓመት ብቻ አልነበረም። የመጀመሪያው ውል ጸድቆ እንዲሠራበት ከመደረጉ በፊት ለዘጠኝ ወራት፤ የሁለተኛው ውል ተዘጋጅቶ እስኪፈረም ድረስ ለአሥር ወራት፤ በድምሩ ሦስት ዓመት ከሰባት ወራት ስትሠቃይ ኖራለች። በእግዚአብሔር ቸርነት የመጀመሪያው ውል ዘመኑ አልቆ እንደምንም ሲፈጸም፤ ለሁለተኛው ስምምነት በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት በኩል ለዝግጅቱ የተደረገው ጥረትና በመጨረሻውም ከብዙ አስቸጋሪ ድርድር በኋላ የተገኘው ውጤት፤ እጅግ የሚያስደስት ብቻ ሳይሆን፤ እጅግም የሚያኮራ ነበር ለማለት ይቻላል።

1. ከዚህ ቀደም እንደተገለጸው የይልማ ዴሬሣ የአሜሪካ ሚሲዮን፤ ለኢትዮጵያ ያስገኘው እርዳታና ድጋፍ፤ የንጉሠ ነገሥቱን መንግሥት ሞራል አጠናክሮታል። ይኸውም በዓለም ላይ ገናና የሆነው የዩናይትድ ስቴትስ ኦፍ አሜሪካ መሪ ፕሬዚዳንት ፍራንክለን ሩዝቬልት፤ ፊቱን ወደ ኢትዮጵያ መልሶ ከለገሣቸው እርዳታዎች ሌላ፤ በሁለቱ አገሮች መካከል በባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ደረጃ የዲፕሎማቲክ ግንኙነት እንዲከፈት በማድረጉ፤ ለኢትዮጵያ ነፃነት ከፍተኛ ማረጋገጫ አበርክቷል። የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ባለሥልጣኖች፤ አሜሪካ በኢትዮጵያ የቆንስላ ቢሮ ከመክፈት በስተቀር፤ ሌላ ተጨማሪ ወጭ ማድረግ አያስፈልጋትም በማለት ሲመክሩ የነበረው ተንኮል ከሸፎባቸው፤ የፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር በአዲስ አበባ ለጋሲዮኑን ከፍቶ ሥራውን ሲጀምር፤ የእንግሊዞች አንጀት ምን ያህል እንዳረረ መገመት ይቻላል። ከእንግዲህ ወዲህ የእንግሊዝ ወታደራዊ አስተዳደር ላለፈው ሦስት ዓመት ከሰባት ወር፤ የኢትዮጵያን የነፃ መንግሥትነት መብት እየደመሰሰ ሲፈጽም የነበረውን የግፍ ሥራ መቀጠል እንደማይችል ተገነዘበው።

2. በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መልካም ፈቃድ በዚያን ጊዜ የሐያ ዘጠኝ ዓመት ዕድሜ የነበራቸውን አክሊሉ ሀብተወልድን፣ የበላይ ሚኒስትሩ ጃንሆይ ሆነው ምክትል የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር አድርገው ሾሟቸው። እ.ኤ.አ በጥቅምት 1943 ዓ.ም ወጣቱ አክሊሉ አዲሱ ሥራቸውን እንደተረከቡ፣ ዋናው ተግባራቸው የመጀመሪያውን የእንግሊዞች ውል ፍጻሜና በምትኩ የሚደረገውን ስምምነት ማዘጋጀት ነበር። ለዚህ ጉዳይ፣ አቶ ይልማ ዴሬሣ ዋሽንግተን በነበሩበት ጊዜ ኢንተርቪዩ አድርገው የቀጠሩት የሕግ ባለሞያ አሜሪካዊው ጆን ስፔንሰር (John Spencer) አዲስ አበባ ደርሶ አዲሱ ሥራውን ሲጀምር፣ በእንግሊዝ አገር በኢንተርናሽናል ሕግ ባለሞያነቱ እጅግ የታወቀው ሚስተር ኖርማን ቤንዊች (Norman Bentwich) ደግሞ፣ ለዚሁ ለሁለተኛው ስምምነት የኢትዮጵያን ፍላጐት ተመርኩዞ አንድ ዓይነት የውል ረቂቅ እንዲያዘጋጅ፣ በልዩ አገልግሎት ማለት ኮንሰልታንት ሆኖ ተቀጠረ።

እንግዲህ በዚህ አኳኋን፣ አሜሪካዊው ጆን ስፔንሰርና እንግሊዛዊው ኖርማን ቤንዊች፣ ለየብቻቸው ባዘጋጁቸው የውል ረቂቆች ላይ፣ ከሁሉ በፊት ለኢትዮጵያ የሚጠቅሙትንና እንግሊዞችንም የማይጐዱትን አንቀጾች እያስማሙ፣ በሁለቱ አገሮች ዘንድ ያለ ችግር ተቀባይነት የሚኖረውን አንድ ዓይነት የውል ረቂቅ ለድርድሩ ለማቅረብ፣ <u>በአክሊሉ ሀብተወልድ ላይ የተጣለ ኃላፊነት ነበር።</u>

ንጉሠ ነገሥቱ ደግሞ ለዚህ ለሁለተኛው ስምምነት ከታላቋ ብሪታንያ ባለሥልጣኖች ጋር ድርድር ለማድረግ የኢትዮጵያ አቋም ምን መሆን እንዳለበት፣ በልዑል ራስ ካሣ የሚመሩት መሳፍንትና መኳንንት በአንድ በኩል፣ ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና ከአቶ መኰንን ሀብተወልድ ጋር የተሰለፉት ወጣት ሚኒስትሮች በሌላ በኩል፣ ከሚያቀርቡላቸው ሐሳቦች ውስጥ <u>የየትኛውን ወገን መርጦ ለመወሰን ችግራቸው ቀላል አልነበረም።</u> ሆኖም፣ የሁለቱም ወገኖች ሐሳብ ችግር ሳይፈጥር፣ በደህና ሁኔታ አስማምተው እንዲፈጸም አድርገዋል።

መሳፍንትና መኳንንት በመሪያቸው በራስ ካሣ አማካይነት ጃንሆይን አጥብቀው ያሳሰቧቸው የሚከተለውን ነበር። " ... እነዚህን እነ ይልማ ዴሬሣንና እነ አክሊሉ ሀብተወልድን የመሳሰሉት ልጆች፣ ምንም እንኳ ለአገር ጉዳይ ያደረባቸው ፍቅርና ለንጉሠ ነገሥታቸው ያላቸው ታማኝነት ባያጠራጥርም፣ በዛሬው ሰዓት ያለንን አቅም በትክክል ባለመመዘን፣ እንግሊዞችን ከያዙት ሥልጣን በሙሉ ማስለቀቅ አለብን እያሉ የሚያሳዩት የእልህ መንፈስ፣ እጅግ የሚያሳስብ ሆኖ ታይቶናል። በተለይ ይልማ ዴሬሣ፣ አሜሪካ ሄዶ ፕሬዚዳንቱን አነጋግሮ ከተመለሰ በኋላ፣ አክሊሉ ሀብተወልድ ደግሞ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴርን ሥልጣን ከያዘ ወዲህ፣ ሁለቱም በአንድነት መኰንን ደስታን ይዘው፣ ስለ እንግሊዞች ውል ጉዳይ የሚናገሩትና እንፈጽማለን ብለው የሚመኙት፣ በአጭር የሚቀጭ ብቻ ሳይሆን፣ በአገራችንም ላይ ሌላ ተደራራቢ ችግር እንደሚያስከትል ያመለክታል።

ከእነዚህ ልጆች ጋር አብረው ሆነው የሚያናፍሱትም፣ እያንዳንዳቸው ከአንድም የሁለት ሚኒስቴሮች ሥልጣን ደርበው የያዙት ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና አቶ መኰንን ሀብተወልድ፣ የሚተልሙት ምን እንደሆን ሊገባን አልቻለም። እነዚህ ልጆች (እነ ይልማ ዴሬሣ) የፈረንጅ ትምህርት የተማሩ ዐዋቂዎች ናቸው ብሎ አብሮ ከመሮጥ፣ ወልደጊዮርጊስና መኰንን የዕድሜያቸውንና የአገልግሎት ዘመናቸውን ፍሬ የሚያሳይ የበሰለ ጥናት ቢያደርጉና ንጉሠ

ነገሥታቸውን ቢረዱ፣ ምን ያህል ጠቃሚዎች በሆኑ ነበር። እኛ ይህንን ሁሉ ካስተዋልን በኋላ፣ ጃንሆይን አጥብቀን ለማሳሰብ የምንፈልገው፣ ዛሬ በአለንበት ሰዓት ከእንግሊዞች ጋር በመልካም ወዳጅነትና ግንኙነት ተሣሥሮ በሰላም ለመኖር ከመድከም በስተቀር፣ ለጠብ ምንም ዓይነት ዕድል እንዳይሰጠው ብርቱ ጥንቃቄ ሊደረግበት ይገባል ብለን ነው።

ከእንግሊዞች ጋር ጃንሆይ በቅርቡ ስለሚያደርጉት ውል ዝግጅቱ እንደምን እንደሆነ፣ ባለፈው ሳምንት የውጭ ጉዳዩን ኃላፊ አቶ አክሊሉን ጠርተን ስንጠይቀው የሰጠን መልስ፣ አስደንጋጭ ሆኖ አግኝተነዋል። " ... እንግሊዞች ሰላምን የሚፈልጉና ክብራቸውን የሚጠብቁ ከሆነ፣ ባለፈው ጊዜ በወታደር ኃይል ያስፈረሙንን ውል ሠርዘን፣ ለጋራ ጥቅማችን አብረን ለመሥራት እንዲያስችለን የምናዘጋጅላቸውን 'አዲስ ውል' መቀበል አለባቸው ... " አለን። እኛ ይህንን አዳምጠን ከፍ ያለ ቅሬታና ይልቁንም ሥጋት ያሳደረብን፣ <u>በሐሳቡና በምኞቱ ላይ ሳይሆን፣</u> የአነጋገሩ አኳኋን ነው። የጃንሆይ የውጭ ጉዳይ ኃላፊ አቶ አክሊሉ ለእኛ እንደገለጸልን፣ እንግሊዞቹንም የማያነጋግራቸው በዚሁ አኳኋን ከሆነ፣ እስከዛሬ ጃንሆይ የደከሙበት የወዳጅነት ግንኙነታችን እንደሚፈርስና ወደ ጠብ እንደምናመራ ጥርጥር የለውም።

እርግጥ ነው! ባለፈው ጊዜ የተፈረመው የመጀመሪያው ውል፣ እጅና እግራችንን አሥሮ ያለ ምንም ሥልጣን መላወስ እንዳንችል ያደረገን መሆኑን እንረዳም። ስለዚህም፣ አዲስ በሚፈረመው ውል ውስጥ ነጻነታችንን ያገዱብንን አንዳንዶቹን አንቀጾች ለማስለወጥ፣ <u>በወዳጅነት መንፈስ</u> መነጋገርና ካስፈለገም በረጋ መንፈስ መሟገት ተገቢ መሆኑን ሁላችንም እናምንበታለን። ይህም ሲሆን፣ አነጋገራችንና የጉዳይ አገላለጻችን የአገሮቻችንን የወዳጅነት ስሜት በሚቀሰቅሱ፣ ትሕትናንና ፍቅርን በሚያሳዩ ቃላቶች እንዲሆኑ ካልተዘጋጀንበት፣ በዛቻና በከረረ አነጋገር የሚመረት ፍሬ አለመኖሩን ማወቅ አለብን። እንግዲህ! ጃንሆይ፣ ለእኛ የታየንንና የመሰለንን አቅርበንልዎታል። እርስዎ ፈጣሪዎ የሚያመለክትዎትንና ፈቃድዎ የሚሆነውን ያድርጉ ... " ሲሉ አስተያየታቸውን አቀረቡ። ከዚህ በላይ በተገለጸው ሐሳብ ሙሉ ስምምነት ያደረጉት መሳፍንትና መኳንንት የሚከተሉት ነበሩ፡፡

- ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ፣ የዘውድ ምክር ቤት ሰብሳቢ፣
- ልዑል መርዕድ አዝማች አስፋወሰን፣ አልጋወራሽ፣
- ልዑል መኰንን ኃይለሥላሴ፣ የሐረር መስፍን፣
- ራስ ብሩ ወልደገብርኤል፣ የከፋ ጠቅላይ ገዥ፣
- ራስ አደፍርሰው ይናዱ፣ የሲዳሞ ጠቅላይ ገዥ፣
- ቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው፣ ጠቅላይ ሚኒስትር፣

የንጉሠ ነገሥቱ የቅርብና ፍጹም ታማኞች ከሆኑት ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ እና ከአቶ መኰንን ሀብተወልድ ጋር የተሰለፉት ወጣቶቹና በዘመናዊ ትምህርት የታነጹት ሚኒስትሮች፣ በኢትዮጵያና በታላቋ ብሪታንያ መካከል ለሚፈረመው ለሁለተኛው ውል ዝግጅት፣ አጥንተው ያቀረቡት ሐሳብ የሚከተለውን ነበር። <u>በወጣቶቹ ሚኒስትሮች አስተያየት፣ ከእንግዲህ ወዲህ በኢትዮጵያና በታላቋ ብሪታንያ መካከል የሚመሠረተው ግንኙነት፣ ወዳጅነትንና የጋራ ጥቅምን በእኩል ደረጃ የሚያስተሳስር መሆን አለበት እንጂ፣ ባለፈው ጊዜ</u>

እንደተከናወነው አንዱ የበላይ ሌላው የበታች ሆኖ የሚታይበት ሁኔታ አይፈጠርም።

የዛሬ ሁለት ዓመት የተፈረመው ውል፤ የሕግና የፖለቲካ ባለሞያዎች የሆኑ የሁለቱ አገሮች መልዕክተኞች ተሠይመው ሳይደራደሩበት፤ ወታደሮቹ ባለሥልጣኖች እነሱ እንዳሻቸው የአገራችንን የአስተዳደር ሥልጣን ይዘው ለመምራት በሚያስችላቸው መንገድ፤ ያዘጋጁት ውል መሆኑን የሚክድ የለም። ለምሳሌ፤ በታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ስም ሆኖ ውሉን ያረቀቀውና የፈረመው፤ በሜጀር ጄኔራል ደረጃ የሚገኝ አንድ የጦር መኰንን ሲሆን፤ በኢትዮጵያ በኩል ንጉሠ ነገሥቱ ራሳቸው እንዲፈርሙ የተደረገው፤ በዚያን ሰዓት ኢትዮጵያ እንደ አንድ ነጻ መንግሥት ተቆጥራ መብቷ ባለመጠበቁ መሆኑን የሚስተው የለም።

የዛሬ ሁለት ዓመት ዓለምን ባጥለቀለቀው የጦርነት ማዕበል፤ ታላላቅ መንግሥታቶች ሁሉ ነፃነታቸውን የሚከላከሉበትና በሞትና በሕይወት መካከል የሚጣጣሩበት ዘመን ስለሆነ፤ በታናናሽ መንግሥታቶች ላይ የሚፈጸመውን ግፍ ለመዳኘት የሚሞከሩበት ጊዜ አልነበረም። የጊዜው ሁኔታ ይህ በመሆኑም፤ የታላቋ ብሪታንያ የዊንስተን ቸርችል የጦር ካቢኔ፤ የኢትዮጵያን ጉዳይ የጦር ባለሥልጣኖቹ በሚመስላቸው መልክ ይዘው እንዲቀዩ መንገዱን ስለለቀቀላቸው፤ ወታደሮቹ በኮሎኒያሊስት መንፈስ በተገነባው አስተሳሰባቸው፤ በአገራችን ላይ የሚያሳዝን በደል ሲፈጽሙ ለመቆየት ተመቻቸው።

ዛሬ ግን የዓለም ሁኔታ ተለውጧል። ምንም እንኳ ጦርነቱ ተፈጽሞ ሙሉ ሰላም ተመሠረተ ባይባልም፤ ታላላቆቹ አገሮች ፋሽስትንና ናዚን እያወደሙ፤ የራሳቸውን ብቻ ሳይሆን የታናናሽ አገሮችንም ነጻነት ለማስከበር የሚያስችል አቅም አግኝተዋል። በዚህም መሠረት የዛሬዋ ኢትዮጵያ፤ ከዛሬ ሁለት ዓመት በፊት የነበረችዋ ኢትዮጵያ አይደለችም። የአራቱ የዓለም ታላላቆቹ አገሮች፤ የአሜሪካና የእንግሊዝ፤ የመስኮብና የፈረንሣይ መንግሥታት በአዲስ አበባ የዲፕሎማቲክ ሚሲዮናቸውን ከፍተው፤ ኢትዮጵያ በኢንተርናሽናል ሸንጐ የቀድሞውን የተከበረ ቦታዋን መረከቧንና የነጻዎቹ የዓለም ቤተሰቦች አባልነቷን አረጋግጠውላታል። ስለዚህ፤ ከታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ጋር ኢትዮጵያ የምትፈራረመው ውል፤ በወዳጅነት መንፈስና የእኩልነትን መብት በያዘ የጋራ ጥቅም ላይ የተመሠረተ መሆን ስላለበት፤ በሚከተሉት ዋና ዋና ጉዳዮች ላይ ተዘጋጅተን እንድንጠብቅ፤ የግርማዊነትዎን ፈቃድ በታላቅ ትሕትና እንለምናለን።

1. ግርማዊነትዎ እንደሚያውቀው፤ እ.ኤ.አ በጥር 31 ቀን 1942 ዓ.ም ከታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ጋር የተፈረመው ውል፤ የጊዜው ገደብ ካለቀ ሦስት ወር ሊሞላው ነው። በእኛ በኩል በስምምነታችን መሠረት፤ የቀድሞው የውል ዘመን መፈጸሙንና በምትኩ ለሚዘጋጀው አዲስ ውል፤ ንግግር እንዲደረግበት የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ከነገ ዛሬ ያስታውቀናል ብለን ስንጠባበቅ ቆይተን ነበር። ነገር ግን እስከአሁን የሰማነው ምንም ነገር የለም። እኛ ተከታትለን እንደደረስንበትና ሁኔታውም እንደሚያሳየው፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ባለሥልጣኖች፤ በተለይም የወታደራዊው አስተዳደር ምኞት፤ በተቻለ መጠን ይኸው የቀድሞው ውል ለሁለት ዓመት እንዲራዘም ማድረግ ነው እንጂ፤ ሌላ አዲስ ውል ለማዘጋጀት የሚያጣድፍ ጉዳይ የለም! የሚል ነው። ስለዚህ፤ በስምምነታችን መሠረት በእኛ በኩል የሦስት ወር ጊዜ ገደብ ሰጥተን፤ የውሉን ፍጻሜ ለማስታወቅና ለአዲሱ

ውል ድርድር ያዘጋጀነውን የሕግ ረቂቅ እያይዘን ለታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ለመላክ የግርማዊነትዎን መልካም ፈቃድ እንጠይቃለን።

2. ግርማዊነትዎ እንደሚያስታውሰው፣ ለአዲሱ ውል ከኢትዮጵያ በኩል የሚቀርበው የመደራደሪያ ዕቅድ፣ በታወቁት የኢንተርናሽናል የሕግ ባለሞያዎች፣ በእንግሊዛዊው ኖርማን ቤንዊችና፣ በአሜሪካዊው ጆን ስፔንሰር የተሰናዳ ስለሆነ፣ የታላቋ ብሪታንያ ባለሥልጣኖች የአዘጋጆዎቹን ደረጃና ከአድልዎ ነጻ የሆነውን ሐሳብ ሊገነዘቡት ይችላሉ የሚል ዕምነት አድሮብናል።

3. ለድርድር የምናቀርበው አዲሱ ውል፣ ካለፈው ስምምነት ጋር ሲተያይ፣ የአሁኑ፣ የኢትዮጵያንና የንጉሠ ነገሥቷን መንግሥት ሙሉ ነጻነትና ሙሉ መብት በሚገባ የሚያረጋግጥ እንዲሆን ተደርጓል። በዚህም መሠረት፣ "ኢትዮጵያ ከጠላት ከተወሰዱት ቅኝ ግዛቶች አንዷ ነች ተብላ፣ በእንግሊዞች ወታደራዊ ባለሥልጣኖች የተሰጣትን የተንኮል ስም፣ በአዲሱ ውል ፈጽሞ ሰርዘነዋል። እንደዚሁም፣ ካለፉት ሦስት ዓመታት ጀምሮ ሲያስቸግረን የቆየው ይኸው የእንግሊዝ ወታደራዊው አስተዳደር፣ አዲሱ ውል ከሚፈረምበት ዕለት ጀምሮ በመንግሥታችን አስተዳደር ጉዳይ ምንም ዓይነት ሥልጣን የሌለው መሆኑን በግልጽ አሳይተናል።

4. የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት፣ በዓለም ጦርነት ምክንያት ይዞት የቆየውን ኦጋዴንንና ሪዘርብድ ኤሪያ (የተጠበቀ ክልል) የተባሉትን ግዛቶቻችንን አስረክቦን እንዲወጣ ጠይቀናል።

5. አዲስ አበባ ላይ የተቋቋመው የእንግሊዝ የጦር ሚሲዮን፣ ዓላማውና ተግባሩ የኢትዮጵያን የጦር ሠራዊት ለማሠልጠንና ለማዘጋጀት መሆኑ የታወቀ ነበር። ነገር ግን የእንግሊዝ ወታደራዊው አስተዳደር በሰጠው ልዩ ሥልጣን፣ እስከዛሬ ድረስ የፈለገውን ሲያደርግ ቆይቷል። ከእንግዲህ ወዲህ ግን፣ የጦር ሚሲዮኑ ከዚህ ቀደም የተሰጠው የዲፕሎማቲክ መብቱ እንደተጠበቀ ሆኖ፣ ለሥራው ቀጥታ ተጠሪነቱ ለግርማዊነትዎ የጦር ሚኒስትር ለራስ አበበ አረጋይ እንዲሆን፣ በአዲሱ ውል ውስጥ አስገብተነዋል።

6. ግርማዊነትዎ እንደሚያውቀው፣ በኢትዮጵያ የታላቋ ብሪታንያ ባለ ሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር፣ ከሌሎቹ አገሮች የዲፕሎማቲክ ሚሲዮን መሪዎች ሁሉ፣ በፕሮቶኮል "ተቀዳሚ እንዲሆን" ባለፈው ውል ውስጥ ገብቶ እስከ ዛሬ ሲሠራበት ቆይቷል። ይህ ጉዳይ የኢትዮጵያን የነጻነት ክብር የሚነካና በተለይም የሌሎቹን መንግሥታት እንደራሴዎች ቅር የሚያሰኝ ስለሆነ፣ በአዲሱ ውል ውስጥ እንዲሰረዝ አድርገነዋል።

7. ከጂቡቲ እስከ አዲስ አበባ የተዘረጋው የፈረንሣይና የኢትዮጵያ የምድር ባቡር ትራንስፖርት ኩባንያ፣ ፈረንሣይ በናዚ ድል ከሆነች በኋላ፣ በታላቋ ብሪታንያ እጅ ተይዞ ሲሠራበት ቆይቷል። አሁን ግን ለኢትዮጵያ እንዲመለስ አስፈላጊ መሆኑን ጠይቀናል።

ግርማዊ ንጉሠ ነገሥት፤

ከታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ጋር የምንደራደርባቸው በአሥራ ሦስት (13) ክፍል ከተመደቡት አንቀጾች ውስጥ፤ ዋና ዋናዎቹ ከዚህ በላይ በሰባት ነጥቦች የዘረዘርናቸው ናቸው። ቀሪዎቹ ስድስቱ ነጥቦች፤ እስካሁን ከእንግሊዞቹ ጋር ተነጋግረን በተግባር ያዋልናቸው ስለሆኑ፤ የሚያስቸግሩን አይደሉም። በዚህ ማስታወሻ ላይ ባመለከትነው መሠረት፤ የግርማዊነትዎ መምሪያ እንደደረሰን አስፈላጊዎቹን እርምጃዎች ለመውሰድ መዘጋጀታችንን በታላቅ ትሕትና እንገልጻለን።

## የዚህ ጥናት ተካፋዮችና አመልካቾች

1. ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ
   የጽሕፈትና የአገር ግዛት ሚኒስትር

2. አቶ መኰንን ሀብተወልድ
   የእርሻ፣ የንግድና የኢንዱስትሪ ሚኒስትር

3. አቶ መኰንን ደስታ
   የፖስታ ቴ.ቴ ሚኒስትር

4. አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ
   የውጭ ጉዳይ ም/ሚኒስትር

5. አቶ ይልማ ዴሬሣ
   የገንዘብ ም/ሚኒስትር

6. ዶክተር አምባዬ ወልደማርያም
   የፍርድ ም/ሚኒስትር

## የንጉሠ ነገሥቱ መምሪያና ውሳኔ*

- የሠራችሁት ሁሉ ማለፊያ ነው።

- አገር ችግር በሚያጋጥማት ጊዜ እንደዚህ እየተሰበሰቡ ሐሳብን ማስተባበርና ተስማምቶ መሥራት ተገቢ ነው። ሆኖም አንዳንድ ጊዜ ስብሰባ ሲበዛ፤ የአድማ ወይም የፓርቲ አሠራር መንፈስ እንዳይፈነጥቅበት መጠንቀቅ ያስፈልጋል። ለዚህ ለእንግሊዞቹ ጉዳያችን ግን፤ የስብሰባችሁ ውጤት ተገቢነቱን አሳይቷል።

- ያቀረባችሁት ሐሳብ እንዲፈጸም፤ ፈቃዳችን ይሆናል። ሆኖም በእኛ በኩል ቅር ያሉንን ሦስት ጉዳዮች ልንገልጽላችሁ ፈቃዳችን ሆኗል።

---

* ከግርማዊነታቸው ልዩ ጽሕፈት ቤት የተገኘ

1ኛ/ ከእንግሊዞች ጋር ያደረግነው የመጀመሪያው ውል ካለቀ ሦስት ወር ከደረሰ፤ እንግሊዞች እንኪያስታውቁን ድረስ ... ብሎ መጠበቅ ለምን አስፈለገ? ... መችም እንግሊዞች ይኸው ውል የተቻለ ያህል ቢቆይላቸው፤ እንደሚደሰቱ የታወቀ ነው። በዚህ ጉዳይ አክሊሉ እንዲያስረዳን ይሁን!

2ኛ/ የኦጋዴንና የሪዘርብድ ኤሪያ ግዛቶቻችን የዓለም ጦርነት እስኪያበቃ ድረስ፤ እንግሊዞች ይዘውት እንዲቆዩ መስማማታችን የታወቀ ነው። አሁን መችም ጦርነቱ አላለቀም። ታዲያ በቅድሚያ መልሱልን ማለታችን ነው? ይኸንን አክሊሉ እንዲያስረዳን ይሁን!

3ኛ/ ይኸንን ለድርድር የሚቀርበውን ረቂቅ ሕግ ያዘጋጁት፤ የታወቁት እንግሊዛዊና አሜሪካዊ ተወላጆች ስለሆኑ፤ እንግሊዞች እንደሚስማሙበት ተስፋ አድርጋችሁ ተናግራችኋል። የሕግ ዐዋቂዎች የሆኑት የኛ ልጆች እነ ሎሬንሶ፤ እነ አክሊሉና እነ አምባዬ ውሉን ቢያዘጋጁት ኖሮ፤ እንግሊዞች ቅር ይሰኙ ነበር ወይ? ይህንንም አክሊሉ እንዲያስረዳን ይሁን!

4ኛ/ ወልደጊዮርጊስ! ራስ ካሣ በዚህ ከእንግሊዞች ጋር ለምናደርገው ውል በጣም ሐሳብ ገብቶታል። አንተው ራስህ፤ አክሊሉንና ይልማን ይዘህ ስለውሉ ዝግጅትና ስለ አሜሪካንም ግንኙነታችን እስካሁን የተደከመበትን ሁሉ እንዲያውቀው አድርግ!

## ለአዲሱ ውል የሁለቱ አገሮች መልዕክተኞች ተሠየሙ

በታላቋ ብሪታንያ እና በኢትዮጵያ መካከል የተፈረመው ውል፤ እ.ኤ.አ ጥር 31 ቀን 1944 ዓ.ም ተፈጽሞ ሦስት ወር ከአለፈው በኋላ፤ እንደገና ለሦስት ወር እንዲራዘምና በዚሁ ጊዜ ውስጥ ተተኪው አዲሱ ስምምነት ድርድር እንዲደረግበት፤ ከኢትዮጵያ በኩል የተዘጋጀውን የሕግ ረቂቅ እያይዘው አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ የውጭ ጉዳይ ም/ሚኒስትር የእንግሊዝን መንግሥት ጠየቁ። በዚያን ጊዜ፤ በአዲስ አበባ የታላቋ ብሪታንያ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ሮበርት ሐው፤ አዲስ ለሚፈረመው ውል ኢትዮጵያውያኖች እጅግ ያሰቡበትና የተዘጋጁበት ስለሆነ፤ ባቀረቡት የሕግ ረቂቅ ላይ አስፈላጊው መሻሻል ተደርጐበት ድርድሩ እንዲጀመር ለሎንዶን ማሳሰቢያ ልኮ ነበር።

የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ አንቶኒ ኤደን፤ ከአዲስ አበባ የቀረበውን ሐሳብ በቀና መንፈስ ሲቀበለው፤ የጦር ሚኒስትሩና የኮሎኒዎች ጉዳይ ሚኒስትር፤ ከኢትዮጵያ በተዘጋጀው የሕግ ረቂቅ ላይ ለመነጋገር ፈቃደኞች አልነበሩም። በተለይም ካይሮ ያለው የታላቋ ብሪታንያ የመካከለኛው ምሥራቅ ጦር አዛዥ ጄኔራል ዊቨልና የምሥራቅ አፍሪካ የጦር ባለሥልጣኖች እነ ሜጀር ጄኔራል ፊሊፕ ሚቸል፣ ኢትዮጵያ እነሱ በሚመሩት ወታደራዊ አስተዳደር ውስጥ መቆየቷ በጣም አስፈላጊ ስለሆነ፤ የቸርችል የጦር ካቢኔ እስከ ጦርነቱ ፍጻሜና የሰላም ጉባኤ እስከሚደረግበት ጊዜ ድረስ እስካሁን የሚሠራበት ውል፤ መቀጠል አለበት ብሎ እንዲወስንላቸው፤ የጦር ሚኒስትሩን ድጋፍ ይዘው ብዙ ጥረት አድርገው ነበር።

ይሁን እንጂ፣ በቸርችል ካቢኔ ምንም ዓይነት ውሳኔ ሳይደረግ፣ በኢትዮጵያ በኩል ውሉ የተራዘመበት የሦስት ወር ጊዜ ማለቂያው ስለደረሰ፣ ኢትዮጵያ ከእንግዲህ ወዲህ ያለፈውን ውል ለማራዘም አለመቻሏን የውጭ ጉዳይ ም/ሚኒስትሩ ለሎንዶን በጽሑፍ አስታወቁ። የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ባለሥልጣኖችም፣ ኢትዮጵያ ከዩናይትድ ስቴትስ ጋር በመቀራረብ ሞራል አግኝታ የጠነከረ አቋም ይዛለች በሚል መንፈስ፣ እ.ኤ.አ በዚህ በመስከረም ወር 1944 ዓ.ም ውስጥ፣ መልዕክተኞቻችንን ልከን የአዲሱን ውል ድርድር እንጀምራለን ሲሉ መግለጫ ሰጡ። በዚህ ጊዜ አክሊሉ ሀብተወልድም የአዲሱን ውል ዝግጅት ለማጠናቀቅ እንዲመቸን፣ የቀድሞውን ውል በሁለት ወር እናራዝመዋለን አሉ።

በዚህ መሠረት እ.ኤ.አ መስከረም 11 ቀን 1944 ዓ.ም፣ በውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ በአንቶኒ ኤደን አቅራቢነት፣ ከኢትዮጵያ ጋር ለሚደረገው ስምምነት **የመልዕክተኞቹ መሪ የታወቀው የዘውድ አማካሪ ኧርል ሎርድ ደላዋር** (Earl Lord De La Warr) **እንዲሆን ጠቅላይ ሚኒስትሩ ዊንስተን ቸርችል አጸደቀ።**

<u>የመልዕክተኞቹም አባሎች፣</u>

| | |
|---|---|
| ከኮሎኒዎች ጉዳይ ሚኒስቴር፣ | ሰር ቢ.ሬይሊ (Sir B.Reilly) |
| ከውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር፣ | ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ሮበርት ሐው፣ (Robert G.Howe) |
| ከጦር ሚኒስቴር፣ | ኮሎኔል ዢ.ጂ ዋልከር (J.G. Walker) |
| ከትሬዠሪ (የገንዘብ ሚኒስቴር)፣ | ሚስተር ዶል (W.A.M. Doll) |

መሆናቸው በይፋ ተነገረ።

ከዚህ በላይ እንደታየው፣ እነዚያ በአገራችን ላይ ያንን ሁሉ የኮሎኒያሊስት ግፍ ሲፈጽሙብን የነበሩት፣ እነ ሜጀር ጄኔራል ፊሊፕ ሚቸልና እነ ብሪጋድየር ሞሪስ ለሽ፣ የመልዕክተኞቹ አባል ሆነው ባለመመረጣቸው፣ ከንጉሠ ነገሥቱ ጀምሮ ከፍተኛ ደስታ ያላደረበት የለም። የመልዕክተኞቹ መሪ እንዲሆን እጅግ የተከበረውን የታላቋ ብሪታንያ የዘውድ አማካሪ ሎርድ ደላዋርን መርጦ ያቀረበው የውጭ ጉዳይ **ሚኒስትሩ አንቶኒ ኤደን፣ ለጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል በጻፈው ማስታወሻ ላይ፣ " ... ሎርድ ደላዋር፣ በአሁኑ ሰዓት ኢትዮጵያን ወደ ኮሎኒ አስተዳደር ለማዛወር የሚፈልጉትን ሰዎች ሐሳብ የማይቀበል ስለሆነ፣ የምንሰጠውን መምሪያ ተከትሎ እንደሚፈጽምልን ተስፋ አለኝ ... "** ሲል አስተያየቱን ገልጿል። ዊንስተን ቸርችልም ወዲያውኑ በሰጠው መልስ፣ "የሎርድ ደላዋር ምርጫ፣ በጣም ጥሩ ነው" ብሎታል።*

ሎርድ ደላዋርና መልዕክተኞቹ መስከረም 26 ቀን 1944 ዓ.ም አዲስ አበባ እንደሚገቡ ሲታወቅ፣ በንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት በኩል አውሮፕላን ጣቢያ ተገኝቶ ስለሚቀበለው ሰው፣ በጃንሆይ ቢሮ መመካከር አስፈልጎ ነበር። ቀደም ሲል፣ ወጣቶቹ ሚኒስትሮች (መኮንን ደስታ፣ ይልማ ዴሬሳ፣ አክሊሉ ሀ.ወ)

* F0371/41453



የዊንስተን ቸርችል የጦር ካቢኔ ዋና መልዕክተኛ ሆኖ የተሾመው ሎርድ ደላዋር አዲስ አበባ ሲገባ፤ ከውጭ ጉዳይ ም/ሚኒስትር ከአቶ አክሊሉ ሀብተወልድ ጋር ሲተዋወቅ፤

ተስማምተው፣ የኢትዮጵያ መልዕክተኞች መሪ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ እንዲሆኑና መልዕክተኞቹም ከእነሱ ከሦስቱ በስተቀር፣ ከጦር ሚኒስቴር ራስ አበበ ስለሌሉ ኮሎኔል ዓቢይ አበበ እንዲተኩ፣ በሕግ ረገድ አንዳንድ እርዳታ ለመስጠት የፍርድ ም/ሚኒስትሩ ዶክተር አምባዬ ወልደማርያም እንዲጨመሩ ለጃንሆይ ማስታወሻ አቀረቡ። ከዚህም ሌላ፣ የወጣቶቹ ሚኒስትሮች አስተያየት ሎርድ ደላዋርን በአውሮፕላን ጣቢያ ለመቀበል፣ የኢትዮጵያ መልዕክተኞች መሪ ከሚሆኑት ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በስተቀር ሌላ አያስፈልግም የሚል ነበር። በመካከሉ፣ የግርማዊነታቸው ልዩ ጸሐፊ አቶ ተፈራወርቅ ጣልቃ ገብተው፣ " ... የእንግሊዝ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ሚስተር ሐው በወዳጅነት መንፈስ እንደአጫወተኝ፣ ኧርል ሎርድ ደላዋር እጅግ የተከበረ የዘውድ አማካሪ ስለሆነ፣ ልዑል ራስ ካሣ አውሮፕላን ጣቢያ ተገኝተው ቢቀበሉት ከፍተኛ ክብርና ደስታ ይሰማዋል ብሎ ነግሮኛል ... " አሉ። ወዲያው፣ ጃንሆይ "ራስ ካሣ በዚህ ሐሳብ ይስማማ እንደሆነ፣ ወልደጊዮርጊስ ሄደህ አማክረው!" ብለው አዘዙ። ልዑል ራስ የቀረበላቸውን ሐሳብ ካዳመጡ በኋላ፣ " ... መጭው እንግዳ የንጉሥ መላክተኛ ሳይሆን በመንግሥት የተወከለ ነው ብላችኋል። ደግሞም እኔ አውሮፕላን መምጫው ድረስ የምሄደው ጃንሆይ የሚቀበሉት መሪ ሲኖር ነው እንጂ፣ ከእናንተ ጋር ለመሰለፍና የናንተን ሥራ ለመጋራት አይደለም ... " በማለት አለመስማማታቸውን አስታወቁ።

ጃንሆይ የራስ ካሣን አስተያየት ከሰሙ በኋላ፣ " ... እንግዲያው፣ ጠቅላይ ሚኒስትራችን ወዲህም የንጉሣዊ ቤተሰባችንና የዘውድ ምክር ቤታችንም አባል የሆነው ቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው ተቀባይ ቢሆንና፣ በተጨማሪም የእንግሊዙ እንደራሴ ለተፈራ ወርቅ እንደነገረው፣ ለሰውየው ክብርና ወግ ሲባል፣ ቢትወደድ መኰንን የመልዕክተኞቻችን መሪ ይሁን ... " ብለው ወሰኑ። ወጣቶቹ ሚኒስትሮች በጣም ተበሳጩ። ወልደጊዮርጊስን ይዘው እንግሊዞቹን በድርድሩ ላይ እንደልባቸው ለመከራከርና ለማሸነፍ እንችላለን ብለው ተስፋ አድርገው ነበር። በቢትወደድ መኰንን መሪነት የሚፈልጉትን ማድረግ እንደማይችሉ ተገነዘቡ። በጃንሆይ መልካም ፈቃድና ትዕዛዝ፣ የኢትዮጵያ መልዕክተኞች የሚከተሉት ናቸው ተብሎ ከገነተ ልዑል ቤተመንግሥት መግለጫ ወጣ።

1. ቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው፣
   ጠቅላይ ሚኒስትር የመልዕክተኞች መሪ፣

2. ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፣
   የጽሕፈትና የአገር ግዛት ሚኒስትር ም/የመልዕክተኞች መሪ፣

<u>መልዕክተኞች፣</u> <u>(በፕሮቶኮል ሳይሆን፣ እንደየሥራቸው አስፈላጊነት)</u>

1. አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ፣
   የውጭ ጉዳይ ም/ሚኒስትር፣

2. አቶ ይልማ ዴሬሣ፣
   የገንዘብ ም/ሚኒስትር፣

3. አቶ መኰንን ደስታ፣
   የፖስታ ቴ.ቴ ሚኒስትር፣

4. ኮሎኔል ዓቢይ አበበ፤
የጦር ሚኒስትሩ ተጠባባቂ፤

5. ዶክተር አምባዬ ወልደማርያም፤
የፍርድ ም/ሚኒስትር፤

6. አቶ ተክሉ ሮሮ፤
የመልዕክተኞቹ ዋና ጸሐፊና ቃለ ጉባኤ ያዥ፤

## የሎርድ ደላዋር ሚሲዮንና ውጤቱ*

የታላቋ ብሪታንያ ዋና መልዕክተኛ አዲስ አበባ ሲገባ በአውሮፕላን ጣቢያ የተደረገለት የደመቀ አቀባበልና፤ ከዚያም በቀጥታ ወደ ገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ተወስዶ ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር ሲተዋወቅ የተከናወነው ሥነ ሥርዓት፤ እጅግ ያስደሰተው መሆኑን በግልጽ ያሳይ ነበር። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ፤ በቤተመንግሥቱ ቅጥር ግቢ ውስጥ ለእንግዳው ልዩ ማረፊያ እንዲዘጋጅለት ቢያደርጉም፤ ሎርድ ደላዋር አዲስ አበባ በሚቀይበት ጊዜ የእንግሊዝ ለጋሲዮን ባለሙሉ ሥልጣን፤ ሚኒስትሩ ባሰናዱለት ቦታ መሰንበትን መርጧል።

እ.ኤ.አ መስከረም 26 ቀን 1944 ዓ.ም፤ የሁለቱ አገሮች መልዕክተኞች ተገናኝተው ሥራቸውን ሲጀምሩ፤ ኧርል ሎርድ ደላዋር የመጀመሪያ መግለጫው፤ " ... ባቀረባችሁልን የመደራደሪያ የውል ረቂቅ ውስጥ አብዛኞዎቹን የምንቀበላቸው ቢሆንም፤ በተለይ ሪዘርቭድ ኤሪያ የተባለው ክልልና የኦጋዴን ግዛት በሙሉ፤ በታላቋ ብሪታንያ አስተዳደር ውስጥ መቆየት ስላለባቸው፤ በእነዚህ በሁለቱ ጉዳዮች ላይ ምንም ዓይነት ድርድር የማናደርግባቸው መሆኑን አስታውቃለሁ ... " የሚል ሆነ። ሎርድ ደላዋር የገለጸው ሐሳብ በድርድር መልክ ሳይሆን፤ የማስፈራሪያን መንፈስ የሚያመለክት ስለሆነ፤ እኔ መልሱን ልሰጠው ሲሉ አክሊሉ ሀብተወልድ የኢትዮጵያን መልዕክተኞች መሪ ጠየቁ። ቢትወደድ መኰንን፤ ገና ሥራችንን ስንጀምር ለጠብ ዕድል መስጠቱ የማይጠቅመን ስለሆነ፤ የሻይ ሰዓት መድረሱን በማስታወቅ ለጊዜው ስብሰባችንን አቋርጠን የግል ውይይት ብናደርግበት ይሻላል አሉ። በሻዩ ግብዣ ላይ ከኢትዮጵያ መልዕክተኞች፤ አክሊሉ ሀብተወልድና ይልማ ዴሬሣ የእንግሊዙን ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ሚስተር ሐውን ይዘው፤ ከሎርድ ደላዋር ጋር ሐሳብ ተለዋወጡ። ይኸውም፤ ሥራችንን ለማፋጠን የሚቀናን፤ ከኢትዮጵያ በኩል የቀረበውን የመደራደሪያ የውል ረቂቅ ለስብሰባችን መነጋገሪያ ሰነድ አድርገን በመቀበል፤ አንቀጽ በአንቀጽ ብንነጋገርበት ይሻላል እንጂ፤ ከውስጡ አንዳንዶቹን ጉዳዮች ለብቻ እያነሣን መከራከሩ፤ ጊዜ የሚገድልብን ይሆናል፤ የሚለውን የኢትዮጵያን መልዕክተኞች አስተያየት አቶ ይልማ ዴሬሣ በእንግሊዝኛ አስረዱ። ሎርድ ደላዋር ይህንን ሐሳብ ወዲያውኑ ስለተቀበለው፤ በዐሥራ ሦስት አንቀጾች የተዘረዘረው ረቂቅ ውል፤ ከሰባተኛው አንቀጽ በስተቀር አንድ በአንድ እየታየ ውሳኔ እንዲሰጠው ስምምነት ተደረገ።

ቀደም ሲል እንደታየው፤ በኢትዮጵያውያኖች በኩል ሚኒስትሮቹ በሙሉ በአገር ፍቅር ስሜት የተባበሩና የሚረዳዱ በመሆናቸው፤ የአገራችንን ክብር የሚነካ

* FO-371/46052

እንዳች እንከን እንዳይፈጠር ብርቱ ጥንቃቄ አድርገዋል። የመጀመሪያው ውል እንዳች ድርድር ሳይደረግበት፣ ኮሎኒያሊስቶቹ የእንግሊዝ የጦር ባለሥልጣኖች በሚፈልጉት ዓይነት ብቻ ተዘጋጅቶ በግዴታ የተፈረመ በመሆኑ፣ በኢትዮጵያውያን ላይ ምሬትና ሐዘን የተቀላቀለበት ማስታወሻ እንደተወ አይረሣም። ዛሬ ግን ይኽ ይደገማል ተብሎ አይታሰብም። ሆኖም፣ ለሁለተኛው ውል የተደረገው ዝግጅት፣ ምንም እንኳ የኢትዮጵያን ሙሉ ነጻነት የሚያረጋግጥና መብቷንም የሚያስከብር ቢሆንም፣ የኢትዮጵያ መልዕክተኞች በጀርባችን የሚጠመጥሙት የእንግሊዞች ተንኮል ምን ይሆን? እያሉ ከመጠራጠር ዕፎይ አላሉም።

በሁለቱ አገሮች መልዕክተኞች መካከል ድርድሩ ከተጀመረ በኋላ፣ የመጀመሪያዎቹ ስድስቱ አንቀጾች ብዙ ክርክር ሳይገጥማቸው ከስምምነት ላይ ተደርሷል። ከነዚህም ውስጥ አምስቱ ዋና ዋናዎቹ የሚከተሉት ናቸው።

1. በኢትዮጵያ፣ የታላቋ ብሪታንያ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር፣ በፕሮቶኮል ከሌሎቹ የዲፕሎማቲክ ሚሲዮን መሪዎች ሁሉ የነበረው "ተቀዳሚነት" ተሠረዘ።

2. አዲስ አበባ ላይ የተቋቋመው የታላቋ ብሪታንያ የጦር ሚሲዮን፣ እስከ ዛሬ ድረስ ሲታዘዝ የቆየው በምሥራቅ አፍሪካ ጦር አዛዥ ሥር ስለሆነ፣ በአዲሱ ውል ተጠሪነቱ ለኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መንግሥት የጦር ሚኒስትር እንዲሆን ተደረገ። የዚህ የጦር ሚሲዮን አዲስ አበባ ላይ የተቋቋመበት ዋናው ዓላማ፣ የኢትዮጵያን ጦር ሠራዊት ለማቋቋምና ለማሠልጠን ሲሆን፣ ለንጉሠ ነገሥቱ የጦር ሚኒስትር አልታዘዝም ብሎ እስካሁን መቆየቱ የሚያስገርም ነበር።

3. ፈረንሣይ በጀርመን ድል ከሆነች በኋላ፣ ከጂቡቲ እስከ አዲስ አበባ የተዘረጋው የኢትዮጵያና የፈረንሣይ የምድር ባቡር ኩባንያ፣ በታላቋ ብሪታንያ ተይዞ እስከዛሬ ድረስ ሲካሄድ ቆይቶ ነበር። አሁን ግን አዲሱ ውል ከሚጸናበት ቀን ጀምሮ ኩባንያውን ለኢትዮጵያ መንግሥት ለማስረከብ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ተስማምቷል። ይህም ርክክብ የሚፈጸመው፣ በኢትዮጵያ በኩል የባቡር ሥራ ባለሞያዎቹ በተሟላ አኳኋን መዘጋጀታቸው በሚረጋገጥበት ጊዜ እንዲሆን ሁለቱም መንግሥታቶች (የኢትዮጵያና የታላቋ ብሪታንያ) ተስማምተዋል።

4. ባለፈው ውል፣ ንጉሠ ነገሥቱ ለልዩ ልዩ ሥራዎች በተለይም፣ ለዳኝነትና ለሕግ አማካሪነት ባለሞያዎችን መቅጠር የሚችሉት ከእንግሊዝ አገር ብቻ እንዲሆን ተወስኖባቸው ነበር። አሁን ግን፣ በአዲሱ ውል ለአገሪቱ አስፈላጊዎች የሆኑትን ለዳኝነትም ሆነ ለሕግ አማካሪነት፣ የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ከእንግሊዝ ብቻ ሳይሆን፣ ከሌሎቹም አገሮች አወዳድሮ ለመቅጠር መብቱ የተጠበቀ መሆኑ ተረጋግጧል።

5. እስከ ዛሬ ድረስ በአየር ትራንስፖርት ረገድ በኢትዮጵያ ላይ የብቸኝነት መብት ወስዶ ሲጠቀም የቆው የብሪቲሽ አየር መንገድ ብቻ ነበር። ከእንግዲህ ወዲህ ግን የኢትዮጵያ መንግሥት ለሌሎቹም አገሮች አየር መንገዶች ፈቃድ ለመስጠት መወሰኑ ታውቆ፣ በስምምነቱ ውስጥ እንዲጠቀስ ተደርጓል።



ለሁለተኛው የእንግሊዞች ውል ዝግጅት ከሎንዶን የመጡት መልዕክተኞች ከኢትዮጵያውያን አቻዎቻቸው ጋር፤



የሁለቱ አገሮች መልዕክተኞች በስብሰባው ላይ፤

# አንቀጽ ሰባት
# ትልቁ አከራካሪ ጉዳይ፤

በቀረበው የውል ረቂቅ ላይ፤ ከአንድ እስከ ስድስት ያሉት አንቀጾች በመልካም መንፈስ እየተወሰኑ አልፈው ሰባተኛው ላይ ሲደርስ፤ ሎርድ ደላዋር በጉባዔው መክፈቻ ንግግር ላይ የሰጠውን መግለጫ በድጋሚ አስታወቀ። ይኸውም፤ በዚህ በሰባተኛው አንቀጽ ላይ ኢትዮጵያ የጠየቀችው፤ የተጠበቀ ክልል የተባለውንና የኦጋዴንን ግዛቴን የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት እንዲያስረክበኝ የሚል ስለሆነ፤ የመልዕክተኞቹ መሪ ሎርድ ደላዋር አለመቀበሉን በቁጣ ቃል ሲናገር፤ ኢትዮጵያውያኖቹም አጸፋውን መልስ መስጠት አለብን አሉ። በዚህ ጊዜ ጠቅላይ ሚኒስትር ቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው ጉዳዮን በረጋ መንፈስ ካልተወያየንበት፤ የየራሳችንን አቋም በማጠንከር የምናደርገው ንግግር መፍትሔ አይሰጠንም የሚል ማሳሰቢያ አቀረቡ። ወዲያው ሎርድ ደላዋር ተነሥቶ ሲናገር፤ "... ሪዘርቭድ ኤሪያ የተባለውና የኦጋዴን ግዛት በታላቋ ብሪታንያ ይዞታ መቆየት ስላለባቸው፤ ድርድር የማናደረግባቸው ጉዳዮች መሆናቸውን ገና ከመጀመሪያው አስታውቀናችኋል። አሁንም ከአቋማችን አንነቃነቅም ... " በማለት ጠረጴዛውን መታ። በዚህ ጊዜ ሦስት የኢትዮጵያ መልዕክተኞች ሐሳባቸውን በየተራ ለመግለጽ ሊቀመንበሩን ጠየቁ።

አክሊሉ ሀብተወልድ፤

" ... በሁለቱ ወዳጆች በሆኑ አገሮች መካከል አንድ ከፍተኛ ስምምነት ለመፈራረም ድርድር በሚደረግበት ጊዜ፤ በተለያየ ሐሳብ ምክንያት ለውሳኔ የሚያስቸግር ጉዳይ ሲያጋጥም፤ ችግሩ የሚፈታው እየተደማመጡ በመነጋገር ነው እንጂ፤ በጉዳዩ ላይ ድርድር ማድረግ አይቻልም ብሎ ገና ከመነሻው በሩን በመዝጋት አይደለም። እርግጥ ነው! ስምምነት የሚዘጋጀው፤ ጠላቶች ሆነው በተዋጉ በሁለት አገሮች መካከል ከሆነ፤ አሸናፊው አቅሙን በመመርኮዝ፤ ይህን እና ይህንን በመሳሰለ ጉዳይ አልደራደርም ብሎ በሩን ሲዘጋ፤ ተሸናፊው ደግሞ ሌላ መንገድ የለኝም በማለት ይቀበል ይሆናል። ነገር ግን፤ የተከበሩ ሎርድ እንደሚያውቁት፤ በእኛ በኢትዮጵያና በታላቋ ብሪታንያ መካከል ይህ ሁኔታ ስለሌለ፤ ምሳሌነቱ አያገለግለንም። ታላቋ ብሪታንያ እና ኢትዮጵያ የቃል ኪዳን ወዳጆች ናቸው። በዚህም መሠረት፤ በመካከላቸው የማይስማሙበት ጉዳይ ሲፈጠር መግባባት የሚችሉት፤ ምክንያቶቻቸውን ተገላልጠው በመነጋገርና አንደኛው የአንደኛውን ችግር በመረዳት ብቻ ነው። ስለዚህም፤ እኛ ኢትዮጵያውያን ወዳጆቻችንን አጥብቀን የምናሳስበው፤ የሪዘርቭድ ኤሪያና የኦጋዴን ግዛታችንን፤ ታላቋ ብሪታንያ ለባለቤቷ ለኢትዮጵያ መመለስ የማትፈልግበትንና ድርድርም አይደረግም የምትልበትን ምክንያት ገልጻ እንድታስረዳን ነው ... " በማለት ንግግራቸውን ፈጸሙ።

ይልማ ዴሬሣ፤

አሁን ጓደኛዬ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ በትክክል እንደገለጸው፤ ታላቋ ብሪታንያ እና ኢትዮጵያ በቃል ኪዳን የተሳሰሩ ወዳጆች ናቸው። ይህም ወዳጅነት ከጊዜ ወደጊዜ እየዳበረና ለጋራ ጥቅማችን ብዙ ፍሬ ያበረክታል ብለን በተስፋና በጉጉት የምንጠባበቀው ነው።



" ... እኛ ኢትዮጵያውያን ወዳጆቻችንን አጥብቀን የምናሳስበው፤ የሪዘርቭድ ኤሪያና የኦጋዴንን ግዛታችንን ታላቋ ብሪታንያ ለባለቤቷ ለኢትዮጵያ መመለስ የማትፈልግበትንና፤ ድርድርም አይደረግም የምትልበትን ምክንያት ገልጻ እንድታስረዳን ነው ... "

አክሊሉ ሀብተወልድ



" ... ጓደኛዬ አክሊሉ ሀብተወልድ እንደ አሳሰበው፤ ለጊዜው ሥራችንን አግዶ የያዘብንን በአንቀጽ 7 ላይ የሠፈረውን ጉዳይ፤ እንቀበልም የሚባልበትን ምክንያት ተግልጥ በመነጋገር ካልፈታነው በስተቀር፤ ሌላ መድኃኒት ልናገኝለት እንደማንችል መታወቅ አለበት ... "

ይልማ ዴሬሣ



" ... ሪዘርቭድ ኤሪያ የተባለውን ክልልና የኦጋዴንን ግዛት፤ እንነጋገርበትም ብሎ በሩን መዝጋት ምን ማለት ነው? ... ይህን የመሰለው ን አቋም የሚወስዱት ለዓለም ሠላም ጠንቆች የሆኑት ዲክታተሮቹ ሂትለርና ሙሶሊኒ ናቸው እንጂ፤ የዓለም ዴሞክራሲ እናት የሆነችው ታላቋ ብሪታንያ አይደለችም። የተከበሩ ሎርድ፤ አስተያየታችንንና ጥያቄያችንን በጥልቀት እንዲያስቡበት እንጠይቅዎታለን ... "

መኰንን ደስታ

እጅግ የተከበሩት ሎርድ ያለ ጥርጥር እንዳስተዋሉትና የሥራ ጓደኛዬ አክሊሉ ደህና አድርጉ እንደተናገረው፤ በአገሮቻችን መካከል ባለፈው ጊዜ የተፈረመው ውል፤ ሁለት ጠላቶች የነበሩ አገሮች፤ አንዱ አሸናፊ ሌላው ተሸናፊ በመሆን ለሰላም የሚያደርጉትን ውል የሚመስል እንጂ፤ በእኩልነትና በጋራ ጥቅም ላይ የተመሠረተ የወዳጅነት ስምምነት አልነበረም። ይህም ሊደርስ የቻለው፤ የፖለቲካና የአገር አስተዳደር ኃላፊዎች በሌሉበት፤ በወታደሮች አስተሳሰብና ሥልጣን ላይ የተመሠረተ በመሆኑ ነው። ዛሬ ግን ያ በዲክታተሮች የተገነባው ውል ፈርሶ፤ በምትኩ ዴሞክራሲንና መብትን የሚመረኩዝ ስምምነት ለመፈራረም እንድንችል፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት እርስዎን የሚያህል የተከበረ ትልቅ ሰው ልኮልናል። በዚህም ንጉሠ ነገሥታችን ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና የኢትዮጵያ ሕዝብ፤ ምን ያህል ደስታና ተስፋ እንዳደረባቸው፤ የተከበሩ ሎርድ ራስዎና መልዕክተኞችዎ እንደተገነዘባችሁት እርግጠኛ ነኝ። ጓደኛዬ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር አክሊሉ ሀብተወልድ እንዳሳሰበው፤ ይህ ለጊዜው ሥራችንን አግዶ በያዘብን በአንቀጽ ሰባት ላይ የሠፈረውን ጉዳይ፤ የማንቀበልበትንና የምንቀበልበትን ትክክለኛውን ምክንያት ተገላልጠን በመነጋገር ካልፈታነው በስተቀር፤ ሌላ መድኃኒት ልናገኝለት አንችልም። ስለዚህ፤ እኔም ከኢትዮጵያ መልዕክተኞች አንዱ የሆንኩት የገንዘብ ሚኒስቴር ኃላፊ፤ የተከበሩ ሎርድ እጅግ ሊያስቡበት ይገባል ብዬ አደራዬን በማጠንከር ንግግሬን እዚህ ላይ አቆማለሁ።

መኰንን ደስታ፤

የዛሬ 14 ዓመት በሐርቨርድ ዩኒቨርሲቲ አንትሮፖሎጂ (Anthropology) በማጠናበት ዘመን አንድ የኢራን ተወላጅ የሆነ ወዳጄ፤ ዛሬ የዩናይትድ ስቴትስ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር "ሄንሪ ስቲምሰን" (Henry Stemson) ስለ ዓለም የፖለቲካ ሁኔታ ንግግር ስለሚያደርግ፤ ሄደን እናዳምጥ ብሎ ጋበዘኝ። የእኔ መስመር እንኳ ፖለቲካ አልነበረም። ሆኖም አጣዳፊ ሌላ ጉዳይ ስለሌለኝ፤ የስቲምሰንን ንግግር ለማዳመጥ ከጓደኛዬ ጋር አብረን ሄድን። የዩናይትድ ስቴትስ የውጭ ጉዳይ መሪ አርባ አምስት ደቂቃ በፈጀው ንግግሩ ውስጥ፤ በአንድ ጉዳይ ላይ የሰጠው አስተያየት አዕምሮዬን ማረከው። " ... በአገሮች ግንኙነት ጉዳይ ፖለቲካና ዲፕሎማሲ ጉን ለጉን የሚሄዱ ናቸው ቢባልም፤ እኔ በግሌ የማስበው፤ የፖለቲካ ጉዳይ በዲፕሎማሲ ሲቀባና ሲፈተግ ከሚሰነብት፤ እውነተኛውን ጉዳይ አውጥቶ መዘርገፍ የተሻለ ፍሬ ይሰጣል ብዬ የማምን ነኝ ... " ብሎ ሲናገር፤ በአዳራሹ ውስጥ ያስተጋባው ጭብጨባ ምን ያህል የጋለ እንደነበረ አስታውሳለሁ። እንግዲህ እኔም፤ በሚስተር ስቲምሰን አስተሳሰብ የተማረክሁ ስለሆንኩ፤ ከእኔ በፊት ከተናገሩት ከሥራ ጓደኞቼ ከአክሊሉና ከይልማ የተለየ አቀራረብ ያሳየሁ እንደሆነ፤ የተከበሩትን ሎርድ በቅድሚያ ይቅርታ እጠይቃለሁ። ይህንንም ስል በአገራችን በኢትዮጵያ ጉዳይ ከሁለቱም ጓደኞቼ አቋምና ሐሳብ የእኔ የተለየ ነው ማለቴ አይደለም። ሁላችንም በአገራችን ጉዳይ የምንከተለውና የምናምነው በንጉሠ ነገሥታችን የተመሠረተውን ፖሊሲና ዓላማ ነው። ይህንኑ መሠረት ይዤ እጅግ ለተከበሩት ሎርድ ደላዋር አንድ ጥያቄ ማቅረብ እፈልጋለሁ። ይህም ጥያቄዬ እርስዎ በሰጡት መግለጫ ላይ ብቻ የተመሠረተ ነው። " ... ሪዘርቭድ ኤሪያ ተብሎ የተከለለውንና የኦጋዴንን ግዛት ለኢትዮጵያ ስለመመለስ ጉዳይ፤ ፈጽሞ ድርድር የማናደርግበት ነው ... " ብለው በሩን ዘግተውብናል። በዚህ ቃል፤

በዚህ አነጋገር ሁላችንም ደንግጠናል። የደነገጥነውም፣ ያልጠበቅነውና ያላሰብነው በመሆኑ ብቻ ነው።

ሪዘርብድ ኤሪያ የተባለውን ክልልና የኦጋዴን ግዛታችንን እንነጋገርበትም ብሎ መዝጋት ምን ማለት ነው? ... አንድ መንግሥት፣ ወዳጁ ለሆነው መንግሥት በአገሬ ላይ ጦር አስፍረህ መጠቀም ትችላለህ ብሎ በውል የሰጠውን ግዛት፣ ተረካቢው ጉዳዩን ከፈጸመ በኋላ፣ የያዝኩትን ግዛት ለባለቤቱ መቼ እንደምመልስለት አላውቅም! በጉዳዩም ላይ መነጋገር አልፈልግም! ብሎ መንገዱን ሲዘጋ ታይቶ አይታወቅም። ይህንን የመሰለውን አቋም የሚወስዱት፣ ለዓለም ጠንቆች የሆኑት ዲክታተሮቹ እነ ሂትለርና እነ ሙሶሊኒ ናቸው እንጂ፣ የዓለም ሕዝብ ዴሞክራሲና የነጻነት መብት ተሟጋች የሆነችው ታላቋ ብሪታንያ አይደለችም። ስለዚህ እኛ ኢትዮጵያውያን ከወዳጆቻችን ከብሪታንያውያን ጋር የምንነጋገረው፣ በግልጽና ዴሞክራሲን በተከተለ ሥርዓት ነው። ጥያቄያችን አንድም ሁለትም አይደለም። አንድ ብቻ ነው። ይኸውም፣ በጊዜያዊ ይዞታ የሰጠናችሁን ግዛታችንን በውላችን መሠረት በተወሰነ ጊዜ ውስጥ እንድታስረክቡን ጠይቀናችኋል። የምትሰጡን መልስ አሁንም በድጋሚ "የምንደራደርበት ጉዳይ አይደለም" የሚል እንደማይሆን ትልቅ ተስፋ እናደርጋለን። ሁላችንም ለኢትዮጵያና ለታላቋ ብሪታንያ ወዳጅነት ኃላፊነት አለብን። የምንፈልገው፣ ማናቸውንም የጋራ ጉዳዮችንን በሰላምና በወዳጅነት ለመጨረስ ነው። ስለዚህም፣ የተከበሩ ሎርድ፣ አስተያየታችንን እንዲረዱልንና ጥያቄያችንን እንዲቀበሉን እንለምንዎታለን።

የአቶ መኰንን ደስታ መግለጫ እንደተፈጸመ፣ ሎርድ ደላዋር ለመናገር በተነሣ ጊዜ፣ ምናልባት የፖስታ ቴ.ቴ ሚኒስትሩ ያደረጉት ንግግር አስቆጥቶት፣ የተጀመረው ድርድር እንዲቋረጥ ለመጠየቅ ይሆናል በማለት፣ ስብሰባውን በሊቀመንበርነት የሚመሩት የጃንሆይ ጠቅላይ ሚኒስትር ሠግተው ነበር። ነገር ግን የሎርዱ አስተያየት ከተጠበቀው በላይ ሰላማዊ ሆነ።

" ... የመጨረሻው ተናጋሪ መኰንን ደስታ ንግግሩን ሲጀምር፣ እኔ በዲፕሎማሲ አሠራር ከሚያምኑት ወገኖች አይደለሁም። ስለዚህም፣ ለምናገረው አስቀድሜ ይቅርታ እጠይቃለሁ ሲል፣ ምን ሊያወርድብን ይሆን? በማለት በጥንቃቄ አዳምጬው ነበር። ነገር ግን ሚኒስትሩ የተናገረው ሁሉ፣ በዲፕሎማሲ ቃላቶች የተቀመሙና በተለይም የሁለቱ አገሮቻችን ግንኙነት በፍጹም ወዳጅነት እንዲቀጥል አጥብቆ የሚያሳስብ በመሆኑ ደስታዬን እገልጥለታለሁ። በመሠረቱ፣ ሦስቱም የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት የካቢኔ ሚኒስትሮች በየተራ የገለጹዋቸው አስተያየቶች በተለያየ መልክ ብዙ ቁም ነገሮችን ያዘሉ ቢሆኑም፣ ግባቸው አንድ ነው። ይኸውም፣ በዚህ አንቀጽ ሰባት ላይ የቀረበውን የሪዘርብድ ኤሪያና የኦጋዴንን ጉዳይ ታላቋ ብሪታንያ ለመደራደር የማትቀበልበት ምክንያት ምን መሆኑ አልገባንም የሚል ነው። ለዚህ ጥያቄ ቅድም ሚኒስትር መኰንን ደስታ በሐርቨርድ ቋንቋው ሲናገር እንደጠቀሰው፣ መልሱ አንድም ሁለትም አይደለም። አንድ ብቻ ነው። ይኸውም፣ የዓለም ጦርነት ተፈጽሞ የዓለም ሰላም እስኪመሠረት ድረስ፣ ሪዘርብድ ኤሪያና ኦጋዴን የተባሉት የኢትዮጵያ ግዛቶች በታላቋ ብሪታንያ እጅ እንዲቆዩ ያስፈልጋሉ የሚል ነው። ለዚህም ኢትዮጵያ ለምታደርገው እርዳታ ታላቋ ብሪታንያ በኪራይ ስም ገንዘብ ለመክፈል ፈቃደኛ ነች። እንግዲህ! ከዚህ የበለጠ ተገልጦ የሚነገር ነገር የለም። መልሱ የእናንተ ነው" ብሎ ዘጋ።

ሎርድ ደላዋር በዚህ አነጋገር አንድ ፍንጭ ሰጠ። " ... ሪዘርቭድ ኤሪያና ኦጋዴን የተባሉት የኢትዮጵያ ግዛቶች ... " የሚለውን ቃል የተጠቀመው ለመጀመሪያ ጊዜ ስለሆነ፣ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መልዕክተኞች፣ ያዳመጡት በከፍተኛ ንቃት ነው። ስብሰባው ሰዓት ደርሶ ከተበተነ በኋላ፣ ከመልዕክተኞቹ መካከል፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ፣ አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ፣ አቶ ይልማ ዴሬሣና አቶ መኩንን ደስታ፣ ለብቻቸው በጽሕፈት ሚኒስትሩ ቢሮ ተሰብስበው፣ አንድ ሐሳብ ነደፉ። ... እንግሊዞች የዓለምን ጦርነት ሰበብ በማድረግ፣ ኦጋዴንንና ሪዘርቭድ ኤሪያ የተባለውን ክልል ይዘው መቆየት የሚፈልጉት፣ በተለመደው የተንኮል ጥበባቸው፣ "ታላቋ ሱማሌ" የሚባለውን አገርና መንግሥት ለማቋቋም እንዲመቻቸው ነው።

እንደሚታወቀው፣ በእንግሊዞች ፕላን ወደፊት "ታላቋ ሱማሌ" የሚባለው አገር ከኢትዮጵያ የኦጋዴንን አውራጃ፣ የእንግሊዝ ሱማሌላንድንና የጣልያን ሶማሊያን፣ ከኬንያ <u>ኤን ኤፍ ዲ</u> የተባለውን የሱማሌ ተወላጆች የሠፈሩበትን አውራጃና የፈረንሣይ ጂቡቲን የሚያጠቃልል ነው። በእነዚህ በተዘረዘሩት አገሮች ውስጥ የሚኖሩት ሕዝቦች ሁሉ፣ በዘር፣ በሃይማኖትና በቋንቋ አንድ ዓይነት በመሆናቸው፣ በታላቋ ብሪታንያ ሞግዚትነት ሲተዳደሩ ከቆዩ በኋላ፣ ጊዜው ሲደርስ ነፃ መንግሥት ሆነው እንደሚቋቋሙ በእንግሊዞቹ ተንኮል ታቅዷል። ይህንን ሁሉ ከግምት ውስጥ በማስገባት፣ አራቱ የኢትዮጵያ ሚኒስትሮች በሰፊው ከተወያዩ በኋላ፣ አንድ ሐሳብ ለደላዋር ለማቅረብ ተስማሙ። ይኸውም፣ " ... በአሁኑ ሰዓት ለሚካሄደው የዓለም ጦርነት፣ የኦጋዴንና የሪዘርቭድ ኤሪያ ግዛታችን ለታላቋ ብሪታንያ ጦር ምንም ዓይነት ጠቀሜታ የማይሰጥ መሆኑን ስለተረዳነው፣ በተወሰነ ጊዜ ውስጥ ግዛታችን እንዲመለስልን ሲሉ ንጉሠ ነገሥቱ አጥብቀው መጠየቃቸውን የተከበሩ ሎርድ ለሚስተር ቸርችል የጦር ካቢኔ እንዲያመለክቱልን እናሳስብዎታለን ... " የሚል ነው። ሎርድ ደላዋር ጥያቄያችንን ተቀብሎ ለማስተላለፍ የሚስማማ ከሆነ፣ ማለፊያ ነው። አይቻለኝም ካለ ደግሞ፣ ንጉሠ ነገሥቱ በቀጥታ ለጠቅላይ ሚኒስትሩ መልዕክታቸውን እንደሚልኩ ይነገረዋል። በመጀመሪያ ግን ለጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል ስለሚላከው መልዕክት፣ የኢትዮጵያ መልዕክተኞች መሪ ቢትወደድ መኩንን እንዳልካቸው ሎርድ ደላዋርን እንዲያነጋግሩት ሚኒስትሮቹ ጠየቋቸው። ጠቅላይ ሚኒስትሩ ጥቂት ካሰቡበት በኋላ፣ " ... ግርማዊ ጃንሆይ በገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ሎርድ ደላዋርን ጠርተው ሻይ በመጋበዝ፣ ይህንን ለሚስተር ቸርችል የሚልኩትን መልዕክት ቢነግሩት፣ በአክብሮት ተቀብሎ የሚፈጽመው ይመስለኛል ... " የሚል ሐሳብ ሰጡ። በዚሁ ሐሳብ መሠረት ሎርድ ደላዋር መልዕክቱን ከጃንሆይ ተቀብሎ ባስተላለፈ በሦስተኛው ቀን፣ የጦር ካቢኔውን መልስ አገኘ። ቃሉም፣ " ... እ.ኤ.አ በጥቅምት 31 ቀን 1944 ዓ.ም የጦር ካቢኔው በሚስተር ቸርችል ሊቀመንበርነት ባደረገው ስብሰባ፣ በኢትዮጵያ የሪዘርቭድ ኤሪያና የኦጋዴን ግዛቶች፣ በታላቋ ብሪታንያ ተይዘው እንዲቆዩ እጅግ አስፈላጊያችን ስለሆነ፣ በነበረው ውል መሠረት እንዲቀጥል መወሰኑን እናስታውቃለን ... " የሚል ነበር።

ሎርድ ደላዋር ከቸርችል የጦር ካቢኔ በደረሰው መልስ ተደስቶ፣ ሥልጣኑ ፈረስ የሚያስጭን መስሎ ታየው። በሚፈረመው ውል <u>በአንቀጽ ሰባት</u> ላይ የሚሰፍረው ቃል፣ " ... የሪዘርቭድ ኤሪያና የኦጋዴን ግዛቶች፣ በታላቋ ብሪታንያ ጦር ኃይል ይተዳደራሉ ... " ከሚል ቃል ውጭ አልቀበልም እያለ <u>ጠረጴዛ መምታቱን ቀጠለ።</u> የኢትዮጵያ መልዕክተኞች ደግሞ የራሳቸውን ሐሳብ ጽፈው አቀረቡ። ቃሉም፣ " ... የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መንግሥት፣ ከታላቋ

ብሪታንያ ንጉሣዊ መንግሥት ጋር ባለቃል ኪዳን በመሆኑ፣ ለዓለም ጦርነት እርዳታ ለማድረግ፣ የገኘነት መብቱ ሳይነካ፣ ኦጋዴንና ሪዘርቭድ ኤሪያ የተባሉትን ግዛቶቹን ይህ ስምምነት ጸንቶ እስከሚቆይበት ጊዜ ድረስ፣ በእንግሊዝ የጦር አስተዳደር እንዲቆዩ ተስማምቷል ... " የሚል ነበር።

እንደተጠበቀው፣ ሎርድ ደላዋር እኔ ከተናገርኩት ቃል ውጭ አልስማማም አለ። የኢትዮጵያ መልዕክተኞችም በሐሳባቸው ጸኑ። በዚህ ጊዜ የእንግሊዙ ዋና መልዕክተኛ ብድግ ብሎ፣ በሐሳብ ተግባብተን መሥራት ስላልቻልን፣ ወደ አገሬ እመለሳለሁ ብሎ ንጉሠ ነገሥቱን ለመሰናበት ቀጠሮ ጠየቀ። ይህም በዛቻ መልክ የቀረበው ጥያቄ፣ የኢትዮጵያን መልዕክተኞች አላሳሰባቸውም። ይልቁንም በአዲስ አበባ ጉዳዩን በቅርብ የሚከታተሉት የአሜሪካና የመስኮብ የዲፕሎማቲክ ሚሲዮን መሪዎች፣ ለኢትዮጵያ አቋም የሚሰጡት የድጋፍ አስተያየት የኢትዮጵያን መልዕክተኞች ሞራል አጠናክሯል። ሎርድ ደላዋር በጠየቀው መሠረት፣ ንጉሠ ነገሥቱ በገነተ ልዑል ቤተመንግሥታቸው ተቀብለው በልዩ ጸሐፊያቸው በአቶ ተፈራወርቅ አስተርጓሚነት በሰፊው አነጋገሩት። በአንቀጽ ሰባት ላይ የሰፈረው ቃል፣ ኦጋዴንና ሪዘርቭድ ኤሪያ የተባሉት ግዛቶች፣ የኢትዮጵያ መሆናቸውን ከመግለጹ በስተቀር፣ ከቀድሞው ውል ምን የተለወጠ ወይም ምን የተቀነሰ ነገር አገኙበት? ... ብለው ጃንሆይ ላቀረቡለት ጥያቄ፣ የታላቋ ብሪታንያ የመልዕክተኞች መሪ አጥጋቢ መልስ አልነበረውም። እንግዲህ! እርስዎ በዚህ ውል አልስማማም ብለው ሰነዱን ሳይፈራረሙ ወደ አገርዎ ለመመለስ ከወሰኑ፣ እኛም ልዩ መልዕክተኞቻችንን ወደ ሎንዶን ልከን ለወዳጃችን ለጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል የገጠመንን እክል ከማስረዳት በስተቀር ሌላ መንገድ የለንም ሲሉ ንጉሠ ነገሥቱ የጠነከረ አቋማቸውን ገለጡ። <u>ሎርድ ደላዋር ለጥቂት ቀናት ካነጋገረ በኋላ፣ በዚህ አከራካሪ ሆኖ ጊዜ በፈጀው በአንቀጽ ሰባት ላይ፣ ከኢትዮጵያ የቀረበውን ሐሳብ መቀበሉን ለንጉሠ ነገሥቱ አስታወቀ።</u> ይህንንም ዜና ለጃንሆይ ነግሮ ከቤተመንግሥቱ ሲወጣ፣ ሚስተር ሞራይቲስ ለተባለው ለሬውተር ዜና ወኪል "ከጃንሆይ ጋር ተስማምተናል" የሚል አጭር መግለጫ ሰጥቶ ወደ ማረፊያው ተመለሰ።

እንግዲህ ታሪክ ተከታታዮችና አንባቢዎች እንደሚያዩት፣ በታላቋ ብሪታንያና በኢትዮጵያ መካከል የተሰናዳው ሁለተኛው ውል፣ እ.ኢ.አ ታኅሣሥ 19 ቀን 1944 ዓ.ም ለመፈረም የበቃው፣ ለሰማንያ አራት ቀናቶች ብርቱ ድርድር ሲደረግበት ከቆየ በኋላ ነው።

| | |
|---|---|
| በኢትዮጵያ ስም፣ | ቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው፣<br>ጠቅላይ ሚኒስትር |
| በታላቋ ብሪታንያ ስም | ኧርል ሎርድ ደላዋር፣<br>የዘውድ አማካሪ |

ለሁለት ዓመት ጸንቶ የሚቆየውን ስምምነት ከተፈራረሙ በኋላ፣ ሁለቱም ወገኖች በየበኩላቸው ሻምፓኝ በመክፈት ደስታቸውን ተገላልጠዋል።

ሎርድ ደላዋር ከጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችልና ከውጭ ጉዳይ ሚኒስትር አንቶኒ ኤደን የተቀበለውን ከፍተኛ ኃላፊነት በመልካም ውጤት ለመፈጸም፣ ምን ያህል ችግር እንደነበረበትና ምን ያህል ጊዜ ማጥፋት እንዳስፈለገው ባቀረበው

ራፖሩ ውስጥ በሰፊው ገልጾታል። ለሦስት ወራት ያህል አዲስ አበባ በቆየበት ጊዜ ውስጥ፣ ኢትዮጵያውያኖች ምን ዓይነት ሰዎች መሆናቸውን ለማወቅና፣ ለአገር ፍቅር የሚቀበሉትን መሥዋዕትነት ተመልክቼ ለማድነቅ ዕድል ሰጥቶኛል ብሏል። ከሁሉም ይበልጥ ደላዋርን ያስገረመው፣ ሪዘርቭድ ኤሪያ የተባለውንና የኦጋዴንን ግዛት ታላቋ ብሪታንያ በጊዜያዊ ይዞታ ለምትጠቀምበት፣ በኪራይ ስም ገንዘብ እንክፈላችሁ ብለን ስንጠይቃቸው፣ ይኸ የአገራችንን <u>የኢትዮጵያን ክብር የሚነካ ነው ብለው አንቀበልም</u> ማለታቸውን ነው። በዚህ ሰዓት የኢትዮጵያ መንግሥት ያጋጠመው የገንዘብ ችግር በመጠኑ የሚገመት አልነበረም። ኢትዮጵያውያኖች ካለባቸው የገንዘብ እጥረት የተነሣ፣ የመንግሥት ሠራተኞቻቸው ከሁለት እስከ አራት ወር የሚደርስ ደሞዛቸውን አልተከፈሉም። ይህ ችግር ወጥሮ ይዟቸው ገንዘብ እንስጣችሁ ሲባሉ፣ የአገራችን ክብርና ነጻነታችን ይበልጥብናል በማለት ለእምቢተኛነት የሚያሳዩት ቆራጥነት የሚበገር አይደለም።

ደላዋር ለውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ለአንቶኒ ኤደን፣ እ.ኤ.አ ጥር 3 ቀን 1945 ዓ.ም ከኢትዮጵያ ጋር ስምምነቱን ካጠናቀቀ ከሁለት ሳምንት በኋላ በጻፈው ሰፊ ራፖር፣ የገለጻቸው ዋና ዋናዎቹ ጉዳዮች የሚከተሉት ናቸው።

**ወዳጄ አንቶኒ፣**

ላይ ላዩን ሲመለከቱት ቀላል የሚመስለውን ይህን ስምምነት ከኢትዮጵያ ጋር እንድደራደር በጠየቁኝ ጊዜ፣ ጉዳዮን እንደዋዛ አይቼው እንደነበረ ልሸሽግዎ አልፈልግም። እንደ ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴራችንም ግምት ሥራው ከአንድ ወር በላይ አይወስድም ተብሎ ነበር። ነገር ግን እኛ እንዳሰብነው ሊሆን እንደማይችል የተረዳሁት፣ በቅድሚያ ካይሮ የነበሩትን፣ ቀጥሎም ናይሮቢ የሚገኙትን የእኛን ሰዎች ስለ ሁኔታው ካነጋገርኳቸው በኋላ ነው። አዲስ አበባ በሚገኘው ለጋሲዮናችን ካሉት ባልደረቦች መካከል፣ ከአሥሩ ሰዎች ዘጠኙ፣ የእኛ ተልዕኮ እንደማይሳካ ያምኑ ነበር። ለዚህ ደግሞ ምክንያቱ አንድ ብቻ አልነበረም። በኢትዮጵያ ላይ ከደረሰው የገንዘብ ችግር በስተቀር፣ ሌሎቹም ሁኔታዎች የእኛን አካሄድ የሚደግፉ አልነበሩም። የነበረን አንድ ተስፋ፣ በዚህ በገንዘብ ችግራቸው ላይ ማተኮር ብቻ ነበር። ይህም ሆኖ <u>"የሪዘርቭድ ኤሪያ ግዛታችንን ከምንለቅላችሁ፣ ገንዘባችሁ ይቅርብን"</u> ብለው ዐረፉት። በእውነቱ የሚገርሙ ሰዎች ናቸው።

እኔ እንደተመለከትኳቸው፣ ኢትዮጵያውያን ለድርድር አይመቹም የሚባለው እውነት ነው። ይኸውም የውጭ አገር ሰዎችን የሚያዩት በብርቱ ጥርጣሬ በመሆኑ ነው እንጂ፣ በችሎታ እጥረት አይደለም። በቅርብ ዓመታት የደረሱባቸውም ሁኔታዎች፣ ይህንን የጥርጣሬ ባሕርያቸውን አባብሶባቸዋል። በዚህ ላይ ደግሞ፣ <u>በተፈጥሮአቸው ኩሩ ናቸው። ከማናቸውም ጥቅም፣ ክብራቸው ይበልጥባቸዋል</u>። እንደሌሎቹ የምሥራቅ አህጉር ሰዎች፣ የመደራደር ችሎታቸው ከፍተኛ ነው። የፈጀውን ጊዜ ይፈጅባቸዋል እንጂ፣ ጊዜ ይወስድብናል ብለው በችኮላ የሚወስኑት ነገር የለም። በቂ ችሎታና ብሩህ አእምሮ ያላቸው ሰዎችም ናቸው። በዚህም ረገድ፣ ከብዙዎቹ የምሥራቅ አህጉር ሰዎች፣ ኢትዮጵያውያኖቹ የተሻሉ ሲሆኑ፣ <u>ችግራቸው ዘመናዊ የሆነው የመንግሥት አስተዳደር ልምድ የሌላቸው መሆናቸው ነው።</u> ስለዚህም፣ ለክብራቸውና ለመልካም ዝናቸው ሲሉ፣ እጅግ የሚያስፈልጋቸውን ገንዘብ በአፍንጫችን ይውጣ ብለው ይመልሳሉ።



በኢትዮጵያና በታላቋ ብሪታንያ መካከል የተዘጋጀው ሁለተኛው ውል ሲፈረም፤
(ቢትወደድ መኮንን እንዳልካቸውና ኧርል ሎርድ ደላዋር)

ገና ድርድሩ እንደተጀመረ፤ ኢትዮጵያውያኖቹ በዚህ በሪዘርቭድ ኤሪያና በኦጋዴን ላይ ያላቸው የአገር ባለቤትነት ስሜት፤ ምን ያህል እንደሆነ ተገንዝቤያለሁ። አዲሱ ኢምፔሪያሊዝም ስለሚያስከትለው ሁኔታ በየሥፍራው የሚናፈሰው ወሬ ኢትዮጵያውያኖቹን ጨርሶ አያሳስባቸውም። በእነሱ አቋም፤ ከዳግማዊ ምኒልክ ዘመነ መንግሥት ጀምሮ የተያዙት ግዛቶቻቸውን፤ በምንም ዓይነት አሳልፎ ለውጭ አገሮች መስጠት እንደ ትልቅ ክህደት የሚቆጠር ነው። በእነሱ ግዛቶች ላይ እኛ ያለን ፍላጐትና የምናገኘው ጥቅም ምን መሆኑን ደህና አድርገው ያውቃሉ። እንዲያውም በአንዳንድ ረገድ፤ ከእኛ የበለጠ ጠንቅቀው ያውቃሉ ማለትም ይቻላል።

የእነሱን ግዛት እኛ ይዘን ለመቆየት የምንሰጣቸው የዓለም ጦርነትና ወታደራዊ ሰበብ፤ ጨርሶ የሚያጠግብ አለመሆኑን ደህና አድርገው ይረዳሉ። ከዚህም የተነሣ በእኛ ሐሳብ ጀርባ የተደበቀው ምን እንደሆነ፤ ለምሳሌም ያህል ስለ ታላቋ ሱማሌ የሚታቀደውን ሁሉ ተከታትለው ደርሰውበታል። ስለዚህ፤ አንድ ጊዜ በግጦሽ መሬት፤ ሌላ ጊዜ በሱማሌዎች ደህንነት እያልን የምንሰጣቸውን ምክንያቶች በጥንቃቄ ካልያዝናቸው፤ በእኛ ላይ ያደረባቸውን ጥርጣሬ እያባባሰው ይሄዳል ብዬ እሠጋለሁ። የእኛን አቋም፤ አሁን በመጨረሻ ከእነሱ ጋር ካደረግነው ስምምነት ጋር ብናመራምረው፤ የኢንተርናሽናል ሕግ ድጋፍ እንደሌለው መታወቅ አለበት። በመሆኑም፤ በእነሱ በኩል ስምምነቱን ጥሰነዋል የሚል ስሞታ አደባባይ ላይ ቢቀርብ፤ በአገራችንና በአሜሪካ ሊያጋልጠን የሚችለውን ሕዝባዊ ተቃውሞ፤ ኢትዮጵያውያኖቹ ደህና አድርገው የሚያውቁት ይመስለኛል። ደግነቱ፤ ወደዚህ ሐሳብ ከማዘንበል፤ ትዕግሥታቸውን የሚያጠነክረው አሁንም ሆነ ወደፊት፤ የእኛ እርዳታ እንደሚያስፈልጋቸው የሚያምኑ መሆናቸው ነው። ዙሪያቸውን የከበብናቸው እኛ ነን። ኤርትራን ለማግኘት የእኛ እርዳታ ያስፈልጋቸዋል። የጦር ሠራዊታቸውን በዘመናዊ መልክ ለማደራጀት፤ የእኛ የጦር ሚሲዮን በጣም ይረዳቸዋል። በተጨማሪም የገንዘብ እርዳታችን እንደሚመኙትም ባይሆን ይጠቅማቸዋል። በዘመናዊ ትምህርትም የብሪቲሽን ሲስተም ያምኑበታል። ለከፍተኛ ትምህርት የሚላኩትም ወጣት ኢትዮጵያውያን ከሌሎች አገሮች ይልቅ፤ እንግሊዝ አገር ነው።

የቴክኒክ አማካሪዎች ለመቅጠር ከሌሎች አገሮች በተለይም ከአሜሪካ ሲያፈላልጉ ይታያሉ። ይሁን እንጂ፤ ከልባቸው የሚመርጡት እንግሊዞችን ነው። ለምሳሌ በኢትዮጵያ መንግሥት ሚኒስትሮች ውስጥ የፀረ ብሪቲሽ ቡድን መሪ የሚባለውን ኃይለኛውን ባለሥልጣን ወልደጊዮርጊስን ስለ አሜሪካኖች እንደዘበት እንሥቼ ሳነጋግረው፤ " ... አሜሪካ የእኛን ጥንታዊ የሆነውን ባሕላችንንና ሥልጣኔያችንን በጥልቀት ለመገንዘብ የሚበቃ ልምድም ችሎታም ያጥራታል። ይሁን እንጂ፤ በምታደርግልን የገንዘብ እርዳታ ዘመናዊውን ሥልጣኔ ለመከተል እንድንችል ዕድሉን ልትከፍትልን ትችላለች ... " አለኝ። በዚህ አኳኋን ነገሩን ስናጠናው፤ ኢትዮጵያውያኖች ለእንግሊዞች ያላቸው ስሜት እየቀዘቀዘ ሄዷል ብለን ልናማቸው አንችልም። እነሱ እንደጠየቁት ጥሩ ጥሩ አማካሪዎች እየመረጥን ልከንላቸው ቢሆን ኖሮ፤ ምክራቸውን እያዳመጡ ለሥራቸውም ዋጋ ይሰጡት ነበር። በእኛ በኩል የደረሰውንም ጉድለት መረዳት አለብን። ቀደም ሲል አማካሪዎች እንድንልክላቸው የጠየቁንን በሚገባ አልመለስንላቸውም። ጠይቀንና እንሰጣችኋለን ያልናቸውን ሰዎች እንኳ፤ ቃላችንን ጠብቀን አልሰጠናቸውም። አንዳንድ የተላኩ አማካሪዎች ቢኖሩም፤ ኢትዮጵያውያኖቹ ለሚፈልጉት ጉዳይ ሁሉም የሚመጥኑ

ሆነው አልተገኙም። ከእነዚህም መካከል እነሱ የወደዷቸው፣ ሳንፎርድንና ሜቴዎስን ነበር። እነሱንም መልሰን ወሰድንባቸው።

ከእንግዲህ ወዲህ ኢትዮጵያ ውስጥ መቆየት ይጠቅመናል ብለን የምናስብ ከሆነ፣ ይህንን ዛሬ የተፈራረምነውን ስምምነት፣ በተግባር ማዋል አለብን። እርግጥ ነው፣ ኢትዮጵያ ለእኛ በጣም ጠቃሚ ለመሆን ትችል የነበረው፣ ንጉሠ ነገሥቱ ፋሽስት ተባርሮ ወደ ሀገራቸው እንደተመለሱ፣ ታላቋ ብሪታንያ ኢትዮጵያን ለሐያ አምስት ዓመታት በሞግዚት አስተዳደር እንድታቆያት የሚያስችል ስምምነት ቢደረግ ነበር። አሁን ይኸ ዕድል አምልጧል። ሌላም ይመጣል ተብሎ አይጠበቅም። ስለዚህም፣ ማሰብና መትጋት ያለብን የወደፊቱን ነው።

እኔ እንዳጠናኋቸው፣ ኢትዮጵያውያኖቹ በአውሮፓ አገሮች መካከል አንዱን ከሌላው አጋጭቶ በመጠቀም ስልት የተካኑ ናቸው። ለዚህ ተንኮላቸው መድኃኒት የሚሆነው፣ እኛ ልናደርግላቸው የምናስበውን ማናቸውንም እርዳታ በቅድሚያ ከአሜሪካኖቹ ጋር እየተነጋገሩ በመወሰን ነው። ... ሌላው አሳሳቢ ሆኖ የሚታየው፣ የዘርና የቀለም ልዩነት ችግር አፍጥጦ መምጣቱ ነው። በዚህ ጉዳይ፣ ስለራሱ ከፍተኛ ግምት የሚሰጠውና ኩሩ የሆነው የኢትዮጵያ ሕዝብ ተደማጭነት ስላለው፣ በእኛ ላይ የጥላቻ ክንዱን ቢያነሣ፣ የአካባቢው አገር ሕዝቦች እንደሚተባበሩት ማሰብ ይኖርብናል። በዚህ በዘር ልዩነት ጉዳይ ንጉሠ ነገሥቱ ከአንድም ሁለት ጊዜ ሲያነጋግሩኝ፣ በእንግሊዞች ቤት ተቀጥረው የሚያገለግሉትም ሆኑ እንግሊዞች በሚያዘወትሩት ሆቴሎችና ቡና ቤቶች የሚሠሩት ኢትዮጵያውያን፣ የእኛ ሰዎች የሚያደርሱባቸው የዘር ልዩነት በደል እጅግ የሚያሳዝን ነው ብለውኛል። ንጉሠ ነገሥቱ በደረሳቸው መረጃ፣ በአሁኑ ጊዜ በአዲስ አበባ የሚደረገው የዘር ልዩነት፣ በኤርትራና በናይሮቢ ከሚታየው ጋር ተመሣሣይ ነው ይባላል። በእውነቱ፣ ይህ ሁኔታ እየታወቀ ችላ መባል የለበትም። እኛ በኢትዮጵያ መቆየትና መሥራት የምንፈልግ ከሆነ፣ ብሪታንያውያን ከዚህ ዓይነቱ አስከፊ ድርጊት መታገድ አለባቸው። አለበለዚያ፣ ችግሩ እየተባባሰ ከሄደ፣ የምንጎዳው እኛ ነን።

ሌላው ጉዳይ ደግሞ፣ ስለ ታላቋ ሱማሌ አመሠራረት የምንይዘውን አቋም በሚቀጥሉት ሁለት ዓመታት ውስጥ ግልጽ ማድረግ ያለብን መሆኑን ነው። ይህንን ስናደርግ፣ ከኢትዮጵያ ወዳጅነትና ከታላቋ ሱማሌ አንዷን መምረጥ ይኖርብን ይሆናል። በምርጫችን ላይ የምናደርገውም ውሳኔ፣ የረዥም ጊዜ ጥቅማችንን ግምት ውስጥ ያስገባ መሆን አለበት። ሁለቱን አማራጮች የሚያስታርቀው፣ የወል አስተዳደር ሥርዓት መመሥረት ሲቻልና ከሁለቱም መካከል አንደኛው የበላይነት ሲኖረው ይመስለኛል። ይሁን እንጂ እኔ እንዳየኋቸው ከሆነ፣ ኢትዮጵያውያኖቹ ከእኛ ጋር ይህንን ዓይነቱን ሽርክና ያቋቁማሉ ማለት ይከብደኛል። ... ለዚህ ሁሉ ከመጨረሻው ውሳኔ በፊት ከአሜሪካኖች ጋር መወያየት ይጠቅማል ብዬ አስባለሁ ። ... "

ሎርድ ደላዋር፣ በሪፖርቱ ፍጻሜ ላይ ለሐሳቡ ማጠቃለያ ሲያቀርብ፣ ከኢትዮጵያ ጋር ባለው የስምምነት ዘመን፣ ታላቋ ብሪታንያ ልትፈጽማቸው የሚያስፈልጉትን ዋና ዋና ጉዳዮች እንደሚከተለው ዘርዝሮ አመልክቷል።

1. ኢትዮጵያውያኖቹ የሚጠይቁትን ጥሩ ጥሩ አማካሪዎች እያዘጋጁ መስጠት፣

2. የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ለኢትዮጵያ ስለሚሰጠው እርዳታ በቅድሚያ ከአሜሪካኖች ጋር መመካከር፣

3. የታላቋ ብሪታንያ ዜጐች በሚኖሩባቸው ማኀበረ ቤተሰቦች ውስጥ መልካም ግንኙነቶች እንዲኖሩ ሁኔታዎቹን ማመቻቸት፣

4. ስለ ታላቋ ሱማሌ የወደፊት ዕድል የተቆረጠ ውሳኔ አድርጐ በይፋ ማስታወቅ ያስፈልጋል ብሏል።

እንግዲህ! ከዚህ በላይ እንደታየው፣ የሎርድ ደላዋር ራፖር የሚያመለክተው ምንም እንኳ ኢትዮጵያኖችን በብዙ ረገድ አደንቃለሁ እያለ በጐ ተግባራቸውን ቢዘረዝርም፣ ለኢትዮጵያ ጥቅምና ዕድገት በጐ አመለካከት እንደሌለው በሚገባ አስገንዝቧል። የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ አንቶኒ ኤደን ለድርድሩ ደላዋርን መርጦ ባቀረበው ጊዜ፣ ኢትዮጵያን ወደ ኮሎኒ ለመመለስ ከሚመኙት ሰዎች መካከል ስላልሆነ፣ እንደምናስበው ይፈጽምልናል ብዬ ተስፋ አደርጋለሁ ብሎ እንደነበረ ይታወሳል። ኤደን እንዳለው፣ በአሁኑ ሰዓት ኢትዮጵያን ወደ ኮሎኒ አስተዳደር ለመመለስ ጊዜው ያለፈ መሆኑን ሎርድ ደላዋር ቢያምንበትም፣ አገራችን ከፋሽስት እንደተላቀቀች ታላቋ ብሪታንያ ለሐያ አምስት ዓመታት በሞግዚት አስተዳደር መያዝ ትችል ነበር ብሎ መቆጨቱን አልሸሸገም። ስለወደፊቷ ኢትዮጵያ ሲናገር፣ አገራችን ከአሜሪካ መንግሥት ጋር ተወዳጅታ ለልማት ዕድገቷ እርዳታ ማግኘቷን ሎርድ ደላዋር ተቃዋሚነቱን በግልጽ አመልክቷል። በዚህ ጉዳይ፣ ታላቋ ብሪታንያ ለኢትዮጵያ አንዳች እርዳታ ከመስጠቷ በፊት፣ ከአሜሪካኖች ጋር መወያየት እጅግ አስፈላጊዋ መሆኑን አጠንክሮ ማሳሰቢያውን ሰጥቷል። በዚህ ሐሳብ የደላዋር ዓላማ፣ አሜሪካኖች ለኢትዮጵያ ረዳቶችና ወዳጆች እንዳይሆኑ በሩን ለመዝጋት መሆኑ በጣም ግልጽ ነው። ስለ ድርድሩም አመራር ሲናገር የሦስት ወራት ጊዜ የፈጀብኝ፣ ኢትዮጵያውያኖች ምቹ ባለመሆናቸው ነው እያለ ደጋግሞ የመሰለውን ሰበብ ሰጥቷል። ደላዋር እንዳለው፣ ኢትዮጵያውያኖቹ ለድርድሩ ምቹ ያልሆኑለት፣ የአገራቸውን ነጻነትና መብት ለማስከበር በመታገላቸው ነው እንጂ እንደሱ በኮሎኒያሊዝም መንፈስ የተበረዙ አስቸጋሪዎችና ጠማሞች ሆነው አይደለም። በተጨማሪም ከኢትዮጵያ በኩል ተደራዳሪዎች ሆነው የቀረቡት፣ ከአሜሪካ ሐርቨርድ፣ ከሎንዶን ስኩል ኦፍ ኢኮኖሚክስ፣ ከፓሪስ ሶርቦን የተመረቁ ባለሞያዎች መሆናቸውን መዘንጋት አይቻልም። እንግዲህ! በዚህ በተፈረመው በ2ኛው ውል፣ ኢትዮጵያ! ከእንግሊዞች የሞግዚት አስተዳደር ስለተላቀቀች፣ ደስታዋ እጅግ የላቀ ነው።

Ref: Public Record Office FO-371/41454
Public Record Office FO-371/41455
Public Record Office FO-371/41457
Public Record Office FO-371/46052
National Archives U.S.A 884. 014/3-2445

# ምዕራፍ ፲

## የቀዳማዊ ኃይለሥላሴና፣ የሩዝቬልት ግንኙነት ዝግጅት

ብላታ ኤፍሬም ተወልደ መድህን በዋሽንግተን የመጀመሪያው የኢትዮጵያ ባለ ሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ሆነው፣ እ.ኤ.አ ታህሣሥ 20 ቀን 1943 ዓ.ም የሹመት ደብዳቤያቸውን ሲያቀርቡ ላደረጉት ንግግር፣ ፕሬዚዳንት ፍራንክለን ዲ.ሩዝቬልት በሰጠው መልስ፣ አንድ ያልተጠበቀ አዲስ ነገር ብልጭ አደረገ። " ... ባለፈው ሰሞን ካይሮ በነበርኩ ጊዜ፣ ከኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ከቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ጋር ተገናኝቼ ለመነጋገር ባለመቻሌ እጅግ አዝኛለሁ። አሁንም ወደፊት በተመቸ ጊዜ፣ ጃንሆይ ወደ አሜሪካ መጥተው ወይም ደግሞ እኔ ወደ ምሥራቅ አገሮች ስጓዝ፣ ተገናኝተን ለመነጋገር እንድንችል እስብበታለሁ ... " ብሉ ተናገረ።

ብላታ ኤፍሬም ይህንን ሩዝቬልት የተናገረውን ይጨብጡና፣ ወዲያውኑ ለጃንሆይ የሚከተለውን ሰፋ ያለ ሪፖርት በኮድ ቴሌግራም ይልካሉ። " ... በአሜሪካ የመጀመሪያው የግርማዊነትዎ ልዩ መልዕክተኛና ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ሆኜ የተሾምኩበትን የክብር ደብዳቤ፣ እ.ኤ.አ ታህሣሥ 20 ቀን 1943 ዓ.ም ለፕሬዚዳንት ፍራንክለን ሩዝቬልት በዋይት ሐውስ ቤተመንግሥት ሳቀርብ፣ ክቡርነታቸው ስለ ግርማዊነትዎ ታላቅ መሪነትና ስለ ኢትዮጵያ ሕዝብ ጀግንነት የተናገሩት ቃል እጅግ የሚያስደስት ነበር። ...

የፋሽስት ጠላት ኢትዮጵያን በግፍ በወረረ ጊዜ፣ ግርማዊነትዎ መጀመሪያ በጦር ሜዳ ራስዎ ተካፋይ ሆነው የፈጸሙትን ተጋድሎ፣ ቀጥሎም በገኔቭ የዓለም መንግሥታት ጉባኤ ላይ በመገኘት፣ ያደረጉትን የዓለምን ሕዝብ መንፈስ የሚቀሰቅስ ንግግር፣ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት በአድናቆት ያስታውሳሉ። እንዲሁም፣ ግርማዊነትዎ ተስፋ ሳይቆርጥ መራራ የሆነውን የስደት ሕይወት አሳልፈው አገርዎንና ሕዝብዎን ነጻ ለማውጣት በመቻልዎ፣ ታሪክ ከፍተኛውን ሥፍራ እንደሚያዘጋጅልዎ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ከልባቸው ያምናሉ። ...

በኢትዮጵያና በአሜሪካ ሕዝብ መካከል ያለውን የወዳጅነት መተሳሰብ ከጠቀሱ በኋላ፣ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት እስካሁን ድረስ ከግርማዊነትዎ ጋር ተገናኝተው ስለ አገሮቻችን ሆነ ስለ ዓለም ሰላም ጉዳይ ለመነጋገር ዕድሉ ሳይገጥማቸው በመቆየታቸው እጅግ ማዘናቸውን በጋለ መንፈስ ገልጠውልኛል። ለምሳሌም ባለፈው ጊዜ ክቡርነታቸው በኢትዮጵያ አካባቢ በነበሩበት ሰሞን፣ ግርማዊነትዎን ለማየት ይችሉ እንደነበረ ካስታወሱ በኋላ፣ ወደፊት ለግርማዊነትዎና ለፕሬዚዳንቱ የሚያመች ጊዜ ሲያጋጥም፣ ጃንሆይ ወደ አሜሪካ መጥተው የኦፊሲየል ጉብኝት እንዲያደርጉና በሰፊው ለመነጋገር እንደምትችሉ፣ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጥልቅ ምኞታቸውንና ፍላጉታቸውን ገልጠውልኛል። ...

እኔም፣ የፕሬዚዳንቱን ንግግር በጥንቃቄ ካዳመጥኩ በኋላ፣ የክቡርነታቸውን መልካም አስተያየትና ያቀረቡትንም ታላቅ ሐሳብ፣ ለግርማዊነትዎ

በፍጥነት በራፖሬ እንደማቀርብ አረጋግጨላችኋለሁ። ፕሬዚዳንቱ በዋይት ሐውስ ቤተመንግሥታቸው እኔን ተቀብለው ይህንን ንግግር ባደረጉበት ጊዜ፣ በዋሽንግተን የግርማዊነትዎ ለጋሲዮን አንደኛ ጸሐፊ የሆኑት አቶ ጌታሁን ተሰማ፣ ከእኔው ጋር አብረውኝ መገኘታቸውን ለግርማዊነትዎ በታላቅ ትሕትና እገልጻለሁ። ... "

ፊርማ ኤፍሬም ተወልደመድህን
የግርማዊነትዎ ታማኝ አገልጋይ

ጃንሆይ ይህ የብላታ ኤፍሬም ራፖር በባሊዝ ዲፕሎማቲክ ደርሷቸው ሲያነቡት፣ ከፍ ያለ ደስታ ይሰማቸዋል። ወዲያውም የራፖሩ ኮፒ ለጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና ለአቶ አክሊሉ ሀብተወልድ በቶሎ ተልኮላቸው፣ በማግሥቱ ጠዋት በ፬ ሰዓት ገነተ ልዑል ቤተመንግሥት መጥተው ንግግር እንዲደረግበት የጃንሆይ ትዕዛዝ ይተላለፍላቸዋል። በቀጠሮው ሰዓት ጃንሆይ የሚከተለውን ተናግረው ሁለቱ ሚኒስትሮች ስለ ጉዳዩ አስተያየታቸውን እንዲሰጡ ይጠይቃሉ። " ... ኤፍሬም ከዋሽንግተን የላከልንን ደብዳቤ ኮፒው ደርሷችሁ እንዳነበባችሁት፣ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት እስከ ዛሬ ድረስ ከእኛ ጋር ተገናኝተው ባለመነጋገራችን፣ በጣም ማዘናቸውንና አሁንም እኛ ወደ አሜሪካ በኦፊሲየል ጉብኝት ሔደን፣ ስለ ራሳችን ግንኙነትና ስለ ዓለምም ሰላም ጉዳይ እንድንነጋገር እንፈልጋለን ብለውታል። ኤፍሬምም ይህንን የፕሬዚዳንቱን ሐሳብ ለእኛ በፍጥነት እንደሚያቀርብላቸው ስለነገራቸው፣ በዚህ ጉዳይ የምንሰጠው መልስ በምን አኳኋን መዘጋጀት እንዳለበት ሐሳብ እንድታቀርቡ የጠራናችሁ ስለሆነ፣ መጀመሪያ ወልደጊዮርጊስ ተናገር! ... " አሉ። ወልደጊዮርጊስ ደግሞ በበኩላቸው፣ በመጀመሪያ የውጭ ጉዳይ ኃላፊው አቶ አክሊሉ እንዲናገሩ አሳሰቡ።

" ... ብላታ ኤፍሬም ያቀረቡት ራፖር መልካም ዜና የሚያበሥር ነው። ይሁን እንጂ፣ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ከጃንሆይ ጋር ለመገናኘት ያላቸውን ፍላጐት ለብላታ ኤፍሬም በመግለጻቸው፣ ከግርማዊነትዎ መልስ አይጠበቅም። ብላታ ኤፍሬም ግን በዚህ ከፕሬዚዳንቱ በተነገረው ቃል መሠረት፣ ከውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ጋር እየተነጋገሩ አስፈላጊው የኦፊሲየል ጥሪ ለግርማዊነትዎ እንዲደርስ ማድረግ አለባቸው ... " ጸሐፊ ትዕዛዝ ወዲያው ቀጠል አደረጉና፣ " ... አሁን አቶ አክሊሉ እንዳለው ብላታ ኤፍሬም ለጃንሆይ ያቀረበው ራፖር በጣም የሚያስደስት ነው። ሆኖም ግርማዊነትዎ አሜሪካን በኦፊሲየል እንዲጐበኙ ጥሪው እስከሚደርስዎ ጉዳዩ በምሥጢር ተይዞ መቆየት አለበት። አለበለዚያ ወዳጆቻችን እንግሊዞች በመሐል ገብተው ሊያደናቅፉብን ይችላሉ ... " የሚል አስተያየት ሰነዘሩ። ቀጥሎም አቶ አክሊሉ የሚከተለውን ተናገሩ። " ... ጃንሆይ እንደሚያስታውሱት፣ ከዛሬ ስድስት ወር በፊት፣ አቶ ይልማ ዴሬሣ በዋይት ሐውስ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልትን ባነጋገረ ጊዜ፣ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ከአሜሪካው መሪ ጋር ለመገናኘት በጣም ያሰቡበት ጉዳይ መሆኑን አስረድቷል። ይልማ በዚህ ብቻ አልቆመም። ከውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ከሚስተር ሑል (Hull) ጋር በሰፊው ተነጋግሮ ተስፋ ያለው መልስ አግኝቶ ነበር። አሁንም፣ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ለብላታ ኤፍሬም በሹመት ደብዳቤ ማቅረቢያ ፕሮግራም ላይ የነገራቸው፣ በዚሁ በይልማ ሚሲዮን ጊዜ የተጀመረውን ንግግር በመቀጠል እንጂ፣ በድንገት አዲስ ነገር ተፈጥሮ አይደለም። ስለዚህ ቀደም ብዬ እንዳሳሰብኩት፣ ከእንግዲህ ወዲህ መደረግ ያለበት ብላታ ኤፍሬም ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት በተነገረው ቃል መሠረት በተቻለ ፍጥነት የጥሪው ደብዳቤ ለግርማዊነትዎ እንዲደርስ ከውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር እየተነጋገሩ ማስፈጸም ብቻ ነው ... " አሉ።



ብላታ ኤፍሬም ተወልደመድኅን
በአሜሪካ የመጀመሪያው የኢትዮጵያ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትርና ልዩ መልዕክተኛ
(Dec. 1943)

ጃንሆይ፤ የጽሕፈትና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሮቻቸው በተናገሩት አልተደሰቱም። ከሁለቱም የተገለጸላቸው አስተያየት፤ የኤፍሬም ተወልደመድህንን ጥረት የሚያቃልል መስሎ ታያቸው። ከልዩ ልዩ አገር የሚደርሰው የቨሊዝ ዲፕሎማቲክ የሚከፈተው በአምሳለ ገነት ጽሕፈት ቤታቸው ስለሆነ፤ ጃንሆይ በመጀመሪያ የብላታ ኤፍሬምን ሪፖርር አንብበው የተረዱት፤ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አሜሪካ መጥተው እንዲያገኟቸው መፈለጋቸውን ለባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትራቸው ስለገለጹ፤ ንጉሠ ነገሥቱ ሐሳቡን በደስታ ለመቀበላቸው በቶሎ መልስ መስጠት የሚጠበቅባቸው መሰሏቸው ነው። በተጨማሪም በአሜሪካ ልዩ መልዕክተኛቸው ብላታ ኤፍሬም፤ ይህንን ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት የገለጹትን መልካም አስተያየት ለማስገኘት በብዙ ደክመውበታል የሚል ዕምነት አድሮባቸዋል። አክሊሉ ሀብተወልድ ደግሞ፤ የዚህ ሥራ ውጤት ከስድስት ወር በፊት በይልማ ዴሬሣ የተደረገው ጥረት ነው በማለት ብላታ ኤፍሬምን ነፃ አወጧቸው። የወልደጊዮርጊስም አስተያየት ወደ አክሊሉ ሐሳብ የሚያመዝን ሆኖ ስለታያቸው፤ የራሳቸውን አቋም በመመርከዝ፤ ጃንሆይ የሚከተለውን መምሪያ ሰጡ።

" … ሁለታችሁም የተናገራችሁትን አዳምጠናል። ሆኖም የኤፍሬም ሥራ በቀላሉ የሚገመት ስላልሆነ፤ ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጋር ስለሚኖረን ግንኙነት እኛው ራሳችን በቀጥታ መምሪያ እየሰጠነው ጉዳዩን ተከታትሎ እንዲያስፈጽም እናደርጋለን። ለጊዜው እናንተ በዚህ በኩል ያለውን ጉዳይ ሌላ ትዕዛዝ እስክንሰጣችሁ ድረስ ለእኛ ተውት … " ብለው አሰናበቷቸው። ይህ የጃንሆይ ውሳኔ ከተሰጠበት እ.ኤ.አ ከጥር 1944 ዓ.ም ጀምሮ፤ ለብዙ ወራት የብላታ ኤፍሬም ተወልደመድህን መንፈስ በጭንቀና በሐሳብ የተወጠረ ነበር። ከገነተ ልዑል ቤተመንግሥት በኮድ ቴሌግራም እየተከታተለ የሚደርሳቸውን የጃንሆይ መልዕክት ከብዛቱ የተነሣ አስቸኳዩንና ጊዜ ሰጭውን እየለዩ ለመሥራት ከፍ ያለ ችግር ሆነባቸው።

ክቡር ብላታ፤ በካዲላክ አውቶሞቢላቸው ላይ የኢትዮጵያን ሰንደቅ ዓላማ እያውለበለቡ፤ ሳያቋርጡ ስቴት ዴፓርትመንት (ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር) በመሄድ፤ አንድ ጊዜ የአፍሪካውን ክፍል ኃላፊ፤ ሌላ ጊዜ የፖለቲካውን ጉዳይ ዲሬክተር፤ አልፎ አልፎም የውጭ ጉዳይ ረዳት ሚኒስትሩን በቀጠሮ እያገኙ፤ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ወደ አሜሪካ መጥተው ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጋር ለመነጋገር ቀጠሮ እንዲወሰንና የኦፊሲየል ጥሪውም ለጃንሆይ እንዲላክ ሲያመለክቱ ከረሙ። የአሜሪካ ስቴት ዴፓርትመንት ኃላፊዎችም፤ የኢትዮጵያን ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር በወግ እየተቀበሉ፤ አንድ ጊዜ ጉዳዩ እየተጠና ነው፤ ሌላ ጊዜ ደግሞ፤ የፕሬዚዳንቱ አገዛዝ በዓለም ጦርነት ምክንያት በሙሉ ተይዞ ከፍተ ቦታ በማጣት ስለሆነ፤ እጠብቁ ጥቂት ታገሡን እያሉ በመደለል ይሸኟቸው ነበር።

ይህንን ከስቴት ዴፓርትመንት በተለያየ መልክ የሚሰጣቸውን መልስ፤ ብላታ ኤፍሬም እያከታተሉ ለጃንሆይ ሪፖርታቸውን ከመላክ ባያቋርጡም፤ ንጉሠ ነገሥቱ ምክንያቶቹን ተረድተው በትዕግሥት መጠበቅ አልቻሉም። አንድ ቀን፤ ከገነተ ልዑል ቤተመንግሥት የተላከ ልዩ መልዕክት ለባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሩ ደረሰ። ቃሉም የሚከተለው ነበር።
ከግርማዊ ጃንሆይ!
ይድረስ ለብላታ ኤፍሬም ተወልደመድህን!

" ... ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት እስከ ዛሬ ድረስ ከእኛ ጋር ተገናኝተው ለመነጋገር ባለመቻላቸው ማዘናቸውንና አሁንም እኛ ወደ አሜሪካ መጥተን እንድናገኛቸው አጥብቀው ያስቡበት መሆኑን ከነገርከን ብዙ ወራቶች አለፉ። አንተ እንደነገርከን፤ እሳቸው ከሐሳባቸው አንቅተው የጠየቁትን፤ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትራቸው በየጊዜው ምክንያት እየደረደረ ቀን ቀጠሮውን የሚያዘገየው ለምን እንደሆነ አልገባንም። እኛ እንደተረዳነው፤ ፕሬዚዳንቱ ሐሳባቸውን የገለጡት ለአንተ ስለሆነ፤ ይህንኑ መሠረት ይዘህ በዋይት ሐውስ ቢሮአቸው ካሉት ረዳቶቻቸው ጋር በመነጋገር፤ ጉዳዩን ማስወሰን ያለብህ አንተ ነህ። ከዚህ ቀደም እንደነገርንህ፤ የኛ ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጋር ተገናኝቶ መነጋገር ለአገራችን ለኢትዮጵያ በጣም ታላቅ ነገር መሆኑን እንዳትዘነጋው! ... "

ይህንን ከንጉሠ ነገሥቱ የተላከላቸውን መመሪያ በታዘዘው መልክ ለመፈጸም ብላታ ኤፍሬምን በጣም ከበዳቸው። ወዲያው የኢትዮጵያ ለጋሲዮን አንደኛ ጸሐፊ የሆኑትን ዲፕሎማት ከቢሮአቸው ጠርተው ምን ማድረግ እንደሚሻል ምክር ጠየቋቸው። አንደኛው ጸሐፊ አቶ ጌታሁን ተሰማ የሚከተለውን አስተያየት ገለጹላቸው። " ... መቸም ላለፈ ክረምት ቤት አይሠራለትም እንደሚባለው፤ ለአለፈ ስሕተትም መጠገኛውን ማግኘት ቀላል አይደለም። ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት የርስዎን የሹመት ደብዳቤ ሲቀበሉ እኔም ተገኝቼ ስለነበረ፤ ያደረጉት ንግግር የዲፕሎማሲ ቃላት እንጂ፤ አንድ የተወሰነ ሐሳብ እንዲፈጸም የሰጡት ማገለጫ ሆኖ የሚቀጠር አልነበረም። ከዚህ ንግግር በኋላ ሪፖርቱን ተቻኩሎ ለጃንሆይ ከመላክ በፊት፤ የአሜሪካ ፕሬዚዳንት ከኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ጋር ለመገናኘት እንዲችሉ ምን ማድረግ እንደሚያስፈልግ፤ ከዋይት ሐውስና ከስቴት ዲፓርትመንት ተነጋግሮ ማጣራት ይገባ ነበር። ይህ ሳይደረግ ሪፖርቱ ቀድሞ ለጃንሆይ ደረሰ። እኔ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ሆኜ ጃንሆይን እንደአየኋቸው፤ አንድ ነገር ከያዙ እስከ መጨረሻው ግብ ድረስ መከታተላቸውን አያቋርጡም። ስለዚህም፤ ለወደፊቱ የሚቻለውንና የማይቻለውን በግልጽ እየለየን ብንነግራቸው ይሻላል እንጂ፤ የሚያስደስተውን ብቻ እየመረጥን ራፖርት ማቅረቡ አንድ ቀን መጥፎ ስሕተት ላይ እንደሚጥለን ማወቅ አለብን። አሁን እርስዎን ላጋጠመዎ ችግር በእኔ በኩል አንድ ሐሳብ መስጠት እፈልጋለሁ።

" ... ጃንሆይና ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት በአሜሪካም ሆነ ወይም በአንድ ሌላ አገር በሚያመች ጊዜ ስለሚገናኙበት ጉዳይ፤ የስቴት ዲፓርትመንትና የዋይት ሐውስ ባለሥልጣኖች ተሰብስበው ለመነጋገር ማቀዳቸውን እርስዎ እንዲያውቁት ተነግሮዎታል። እርስዎ ግን በዚህ ጉዳይ ላይ ለጃንሆይ ሪፖርት አላኩም። ስለዚህ፤ ፩ኛ፤ የሁለቱ ክፍል ኃላፊዎች ተሰብስበው እስከሚነጋገሩና የሚያቀርቡትም ሐሳብ እስከሚጸድቅ ድረስ፤ ጊዜ የሚወስድ መሆኑን ለጃንሆይ ማስረዳት ያስፈልጋል። ፪ኛ፤ ደግሞ በተጨማሪ ጃንሆይን ማሳሰብ ያለብዎት፤ ግርማዊነታቸው ከፕሬዚዳንቱ ጋር ሲገናኙ፤ በምንና በምን ጉዳዮች ላይ ለመነጋገር እንደሚፈልጉ አጀንዳቸው ተዘጋጅቶ እንዲላክልዎ መጠየቅ የተገባ ይሆናል። ስለ አገራችን አሠራር ሁላችንም እንደምናውቀው፤ ይህን የመሰለውን የመሪዎች መነጋገሪያ አጀንዳ ለማዘጋጀት ልምዱ ስለሌለ፤ ረዥም ጊዜ ይጠይቃል። ይህ ጉዳይ ተጠናቆ እስከሚላክልዎ ድረስ፤ እርስዎም ከገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ከሚደርስዎ "የከድ ጉርፍ ጥቂት ጊዜ እፎይ ይላሉ ... "

ይህ ከዚህ በላይ የታየውን ከአንደኛ ጸሐፊው የቀረበውን ሐሳብ ብላታ ኤፍሬም በደስታ ከተቀበሉ በኋላ፣ በራሳቸው ብዕር ኮዱን አዘጋጅተው የሚከተለውን ቃል ለግርማዊ ንጉሠ ነገሥት አስተላለፉ።

**ለግርማዊ ጃንሆይ፣**

" ... ከግርማዊነትዎ በተላለፈልኝ ትዕዛዝ መሠረት፣ ጉዳያችን በተቻለ ፍጥነት እንዲፈጸም የዋይት ሐውስን ቤተመንግሥት ኃላፊዎች ከማትጋት አላቋረጥኩም። አሁን በመጨረሻው እንደተነገረኝ፣ የዋይት ሐውስ ቤተመንግሥትና የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ዋና ዋና ባለሥልጣኖች የጋራ ስብሰባ አድርገው፣ ግርማዊ ጃንሆይና ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ስለሚገናኙበት ቀንና ቦታ በማጥናት ሐሳብ እንዲያቀርቡ ታዘዋል። ግርማዊነትዎ እንደሚገምተው እነዚህ ሰዎች ተሰብስበው እስከሚያጠኑና ከዚያም የጥናታቸው ውጤት ለበላይ ቀርቦ እስከሚጸድቅ ድረስ፣ ጥቂት ጊዜ መጠየቁ የማይቀር ይመስለኛል። በተጨማሪ የሚታሰብበት ሌላው ትልቁ ጉዳይ፣ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትና የአሜሪካው ፕሬዚዳንት ሲገናኙ፣ ግርማዊነትዎ ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጋር ለመነጋገር የሚፈልጓቸውን ዋና ዋና ቁም ነገሮች አዠንዳ ላይ ማዘጋጀት አስፈላጊ ስለሆነ፣ ተጠንቶ እንዲቀርብለት የፖለቲካው ሹም የጠየቀኝ መሆኑን በታላቅ ትሕትና አመለክታለሁ።

ፊርማ ኤፍሬም ተወልደመድህን
የግርማዊነትዎ ታማኝ አገልጋይ

ክቡር ብላታ፣ ከዚህ በላይ የተገለጸውን መልዕክት ወደ አዲስ አበባ ካስተላለፉ በኋላ፣ የሰላም ዕንቅልፍ በማግኘታቸው በጣም ደስ ብሏቸው ነበር። ምን ይሆናል? ይህ ሰላምና ደስታ ከሁለት ሳምንት በላይ ሊቆይላቸው አልቻለም። ጃንሆይ ከብላታ ኤፍሬም በተጠየቀው መሠረት፣ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴራቸውን ሌት ተቀን በማሠራት፣ ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጋር የሚነጋገሩባቸውን ዋና ዋና ጉዳዮች ዘርዝረው ለባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትራቸው ላኩላቸው።

**ከግርማዊ ጃንሆይ!**
ይድረስ ከብላታ እፍሬም ተወልደመድህን
ዋሽንግተን ዲ.ሲ፣

" ... ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጋር በምንገናኝበት ጊዜ፣ በእኛ በኩል ፕሬዚዳንቱን የምናነጋግራቸው በምንና ምን ጉዳዮች ላይ መሆኑን እንድናስታውቅ ተጠይቀያለሁ ስላልክ፣ ይኸው ዝርዝሩ ከዚህ ጋር ተያይዞ እንዲደርስህ አድርገናል። ይህ ዝርዝር ጉዳይ እኛና ፕሬዚዳንቱ ተገናኝተን እስከምንነጋገርበት ጊዜ ድረስ፣ በብርቱ ምሥጢር ተጠብቆ እንዲቆይ ማድረግ አለብህ። እንደዚሁም፣ የፖለቲካው ኃላፊ የእኛን በኩል አዘጋጅተን እንድንሰጥ እንደጠየቀህ ሁሉ፣ አንተም ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ከእኛ ጋር ለመነጋገር የሚያስቧቸው ዋና ዋና ጉዳዮች ምንና ምን መሆናቸውን ጠይቀህ እንድትልክልን ይሁን! . . . "

ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሩ ያልጠበቁት ድንጋጤ ደረሰባቸው። በመጀመሪያ፣ ጃንሆይ ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጋር የሚነጋገሩባቸው ጉዳዮች እንደዚህ እጅግ አስቸኳይ በሆነ መንገድ ተዘጋጅቶ ይመጣል ብለው አልጠበቁም

ነበር። ከዚሁ ጋር የተያያዘው ትልቁ አስደንጋጭ ትዕዛዝ ደግሞ፣ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ከጃንሆይ ጋር የሚነጋገሩባቸውን ጉዳዮች በቅድሚያ እንዲያስታውቁ ይጠየቅ! መባሉ ነው። ይህ እንዴት ይቻላል? በማለት በጣም ተጨነቁ። ሌሊቱን በሙሉ እንቅልፍ አጥተው ሲነጋባቸው፣ እዚህ ጣጣ ውስጥ የጨመረኝ ዋና ጸሐፊው አቶ ጌታሁን ተሰማ ነው ብለው አዘኑ። ጌታሁን የዚህን "አጀንዳ" ጉዳይ ባያመጣብኝ ኖሮ ይህን ዓይነቱ አስቸጋሪ ትዕዛዝ አይወድቅብኝም ነበር።

አሁን ያለኝ አንድ መንገድ ብቻ ነው። ለዚያ ለወዳጂ ለልጅ አክሊሉ ሀብተወልድ ችግሬን ገልጬ በግል ደብዳቤ ላመልክተውና እሱ በቅንነቱ የሚችለውን ያድርግልኝ! ሌላ የማምነው ወዳጅ የለኝም። አክሊሉ ተሚግቶ ሊያድነኝ ካልቻለ፣ የጃንሆይ የሽረት ደብዳቤ እስኪደርሰኝ ድረስ ከቢሮዬ አልንቃነቅም። ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴርም እየሄድኩ ማንንም አላስቸግርም የሚል ውሣኔ ካደረጉ በኋላ፣ ለኢትዮጵያ ውጭ ጉዳይ ም/ሚኒስትር የሚከተለውን ጽፈው ላኩ።

**ወዳጄ የማስብህ ልጅ አክሊሉ!**

በጤናህ ደህና ነህልኝ ብዬ ተስፋ እያደረግኩ፣ የደረሰብኝን ችግር አመለክትሃለሁ። አንተም በማውቀው ደግነትህ የሚቻለውን ሁሉ በማድረግ ከጃንሆይ እንደምታስታርቀኝ ከልቤ አምንሃለሁ። እኔ በረጅሙ የአገልግሎት ዘመኔ ጃንሆይን ዋሽቻቸው አላውቅም። እንደምታውቀው በዚህ በፕሬዚዳንት ሩዝቬልትና በጃንሆይ ግንኙነት ጉዳይ የገባሁበት ጣጣ፣ ሕይወቴን ሰላም አሳጥቶታል። ጠዋትና ማታ ከጃንሆይ የሚደርሰኝ ትዕዛዝ፣ ... ታዲያስ! የእኛና የፕሬዚዳንቱ ቀጠሮ በምን ተወሰነ? ... ትናንት ምን ሠርተህ ዋልክ? ዛሬስ ምን ታደርጋለህ? ... የሚል ስለሆነ፣ ጭንቀቴን ለዋናው ጸሐፊ ለአቶ ጌታሁን አማከርኩት። እሱም ጥቂት አስቦ፣ ፋታ ለማግኘት ከፈለጉ ጃንሆይ ከፕሬዚዳንቱ ጋር የሚነጋገሩባቸው ጉዳዮች ተዘርዝረው እንዲቀርቡ ከፖለቲካው ሹም ተጠይቋል ብለው ይጻፉ አለኝ። ይህም ሲሆን፣ ጉዳዩ ተጠንቶ ከአዲስ አበባ ወደ ዋሽንግተን እስኪላክ ድረስ ረጅም ጊዜ ስለሚወስድ፣ ምናልባትም በዚሁ መካከል የሁለቱ መሪዎች መገናኛ ቀጠሮ ይወሰንና ይገላገሉታል ብሎ መከረኝ። በዚህ ምክር መሠረት ጥያቄውን ጽፌ አስተላለፍኩ። ነገር ግን ባላሰብኩት መንገድ ሁለት ሳምንት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ፣ የጃንሆይ አጀንዳ ተዘጋጅቶ ደረሰኝ። ትልቁ ችግሬ የጠየቅኩት በጣም ፈጥኖ ስለደረሰኝ ብቻ አይደለም። ከዚሁ ጋር የተላከልኝ ትዕዛዝ፣ " ... ፕሬዚዳንቱ ከጃንሆይ ጋር ስለሚነጋገሩበት ጉዳይ ጠይቀህ እንድታቀርብ ... " የሚል በመሆኑ ነው። እንደምታየው ከሁሉም አስጨናቂው ነገር ይኸ ነው። ጉዳይ ያላቸው ጃንሆይ ሆነው ሳለ፣ እንዴት ተደርጉ ፕሬዚዳንቱ መነጋገር የሚፈልጉትን አስቀድመው ያመልክቱ ተብሎ ይጠየቃል? ለስቴት ዴፓርትመንት ሆነ ለዋይት ሐውስ ይህን ጥያቄ ማቅረብ አልችልም። በሌላ በኩል ደግሞ፣ እኔ ነገሩን በልቤ ይዤ ዝም ብል፣ ጃንሆይ መልሱ ሲዘገይባቸው አዲስ አበባ ያለውን የአሜሪካኑን ሚኒስትር የጠየቁትስ እንደሆነ? ብዬ በጣም ሠጋሁ። ስለዚህ፣ የሠራሁትን እውነቱንም ሁሉንም ምንም ሳልቀንስ ምንም ሳልጨምር ለአንተ ለማምንህ ወዳጄ ልንገርህና ከጉዱ አውጣኝ ብዬ እለምንሃለሁ። ታስታውሰው ይሆን? ... አንተ ፓሪስ ተማሪ ሆነህ እኔ ቆንስል ሆኜ ከወንድምህ ከክቡር አቶ መኰንን ጋር ግጭት ገጥሞኝ፣ አንተ ደብዳቤ ጽፈህ እንዳስታረቅከኝ ? ... እኔ ውለታህን አልረሣሁትም። አሁንም ለጃንሆይ አንተ ትደርስልኛለህ ብዬ እተማመንብሃለሁ። የቅን ሰዎች አምላክ ይጠብቅህ።

ፊርማ ወዳጅህ ኤፍሬም ተ.መ

ብላታ ኤፍሬም ለአቶ አክሊሉ የጻፉትን የግል ደብዳቤ አጋጣሚ ሆኖ በአንድ ወደ አዲስ አበባ በቀጥታ በሚጓዝ አሜሪካዊ ዲፕሎማት በኩል ከላኩ በኋላ መልሱን በመጠባበቅ ላይ እንዳሉ፣ ከስቴት ዴፓርትመንት (ከውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር) ስልክ ተደውሎ፣ ረዳት ሚኒስትሩ በነገታው ጠዋት በአራት ሰዓት ሊያያቸው እንደሚፈልግ ተነገራቸው። ብላታ የተሰጣቸውን ቀጠሮ በደስታ ከተቀበሉ በኋላ፣ ጊዜው ደርሶ ለምን ጉዳይ እንደሆነ እስከሚረዱት ድረስ መጨነቃቸውና ማሰባቸው አልቀረም ነበር። በአንድ በኩል መንፈሳቸው ከሐሳብ መለየት ባይችልም፣ ምንም ቢሆን የውጭ ጉዳይ ረዳት ሚኒስትሩ ደስ ለሚያሰኝ ነገር ካልሆነ በስተቀር፣ ራሱ ደውሎ እንዲህ በቶሎ አይጠራኝም ነበር፣ በሚል አስተሳሰብ ራሳቸውን በራሳቸው ሲያጽናኑ አደሩ።

በማግሥቱ ጠዋት፣ ያች የቀጠሮ ሰዓት እንደምንም ደረሰች። ለወትሮው ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሩ ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ሲጠራ፣ ከዋናው ጸሐፊ ጋር አብሮ ይሔድ ነበር። አሁን ግን ብላታ፣ በምክትላቸው ዲፕሎማት ላይ አግባብ የሌለው ቅሬታ በማሳደራቸው፣ ብቻቸውን መሔድን መረጡ። ከረዳት ሚኒስትሩ ቢሮ ሲገቡ፣ አቀባበሉ ከልማዱ የበለጠ የጋለ ሆነባቸው። እንደዚህም ከሆነ ያለ ጥርጥር ለመልካም ዜና ነው የተጠራሁት ብለው ማሰብ ጀመሩ። በንግግሩ ሰዓት ረዳት ሚኒስትሩ አጠገቡ የአፍሪካው ክፍል ኃላፊ እንዲገኝ አድርጓል። ብላታ ምክትላቸውን ትተው ብቻቸውን በመምጣታቸው ኋላ ቆጫቸው። ረዳት ሚኒስትሩ የኢትዮጵያን የዲፕሎማቲክ ሚሲዮን መሪ ለምን እንደጠራቸው ሲናገር፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ስለሚገናኙበት ጉዳይ መሆኑን በቅድሚያ ካስታወቀ በኋላ፣ የሚከተለውን አስረዳቸው።

" ... የአገሮቻችን መሪዎች የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትና የዩናይትድ ስቴትስ ፕሬዚዳንት ተገናኝተው ለመተዋወቅና በጋራ ጉዳዮቻቸውም ላይ ሐሳብ ለመለዋወጥ ተመሳሳይ ስሜታቸውንና ፍላጐታቸውን እንደገለጡ፣ ሁላችንም እናውቃለን። የመሪዎቻችንን ሐሳብ ለመፈጸም ሁላችንም በየበኩላችን የተቻለንን ያህል ጥረት ማድረጋችን አልቀረም ነበር። ነገር ግን ዛሬ የአለንበት ዓለም የመከራ እንጂ፣ የሰላም መሆን አልቻለም። በዚህም ምክንያት ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ሰላምን እንዲያስገኙ፣ ከመላው ዓለም ሕዝብ የተጣለባቸው አደራና ኃላፊነት ፋታ የሚሰጣቸው አልሆነም። በዓለም ላይ የሚካሄደውን ጦርነት በየዕለቱ ብቻ ሳይሆን፣ በየሰዓቱ መከታተልና እርምጃ መውሰድ ግዴታቸው ሆኗል። ስለዚህ፣ የዓለምን ሕዝብ ሰላም የነሣው ይህ ክፉ ጦርነት እስኪበርድና የሰላም ሕይወት ጉዳና እስኪከፈት ድረስ፣ የወዳጅ አገሮችን የእርስ በእርስ ግንኙነት ጉዳይ ለመከታተል የሥራው ውጥረት ጊዜ አልሰጣቸውም።

ከጥቂት ወራት በፊት ፕሬዚዳንቱ ለርስዎ እንደገለጹልዎ፣ ከቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ጋር በዋሽንግተን ወይም በሌላ ቦታ ለመገናኘት ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት መልካም ፍላጐት ቢኖራቸውም፣ በዚህ በተፋፋመው የጦርነት ሰዓት ለመፈጸም የሚመቻቸው አልሆነም። ይሁን እንጂ፣ እኛ የውጭ ጉዳይና የዋይት ሐውስ ኃላፊዎች እንደምናስበው፣ ሲሆን በዚህ በአለንበት ዓመት በ1944 ዓ.ም መጨረሻ ላይ፣ ቢበዛ ደግሞ በመጭው 1945 ዓ.ም መጀመሪያ ላይ፣ ሁለቱ መሪዎቻችን የሚገናኙበትን መንገድ ለማዘጋጀት እንደምንችል ሙሉ ተስፋ አድርገናል። ስለዚህ፣ ዛሬ እርስዎን ጠርቼ ለማነጋገር የፈለግኩት፣ ይህንን ጊዜው የፈጠረብንን ችግር በጥልቀት በማየት፣ ከፍ ካለ ይቅርታ ጋር ለንጉሠ ነገሥት ኃይለሥላሴና ለመንግሥታቸው እንዲያስረዱልን ነው። በአዲስ አበባ ያለውም የርስዎ አቻ

ሚኒስትር ካልድዌል፣ በዚህ ጉዳይ ላይ የደረስንበትን ሁኔታ እንዲያውቀውና እሱም በበኩሉ አስፈላጊውን እንዲያከናውን መምሪያውን እንልክለታለን። በመጨረሻም እርስዎ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሩና እንደኛው ጸሐፊ ሚስተር ተሰማ (ጌታሁን ተሰማ) ከስቴት ዴፓርትመንት ጋር ለምታደርጉት ቅንነትና ትጋት ለተመላበት የዲፕሎማቲክ ጥረት፣ ከፍ ያለ ምስጋና እንዳቀርብልዎ ከሚኒስትራችን ከሚስተር ሑል ታዝዣለሁ ... " በሚል የዲፕሎማሲ ንግግር ብላታ ኤፍሬምን አሰናበታቸው።

የጃንሆይ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር፣ ከስቴት ዴፓርትመንት ረዳት ሚኒስትር ጋር ተነጋግረው ሲወጡ፣ ለጊዜው ወዴት እንደሚሄዱ ግራ ገብቷቸው ነበር። የሰማሁት መልካም ዜና አይደለም። ይህንን ለጃንሆይ ለመጻፍ አቅም ያንሰኛል። ደግሞም ከእኔ በፊት አዲስ አበባ ያለው የአሜሪካ ሚኒስትር ጃንሆይ ዘንድ ቀርቦ ለእኔ የተነገረውን ሁሉ እንሚያስረዳቸው እርግጠኛ ነኝ። ... በማለት፣ ወደ መኖሪያ ቤታቸው ሄደው ዕረፍት ለማድረግ ወሰኑ። በማግሥቱ ዕንቅልፍ በማጣት ሲሰቃዩ አድረው ስለነበረ፣ ሐኪማቸውን ሲያዩት ለአሥራ አምስት ቀን ፀጥ ያለ ዕረፍት ማድረግ አስፈላጊ ነው ብሎ ማስረጃ ጻፈላቸው። ጃንሆይም ብላታ ጤና ማጣቸውን እንደሰሙ፣ ሞራልን ከፍ የሚያደርግ የመልካም ምኞት ቴሌግራም ስለላኩላቸው፣ በጣም ተደስተው ሰነበቱ። ከዚያም የዕረፍት ጊዜያቸውን ፈጽመው እቢሮአቸው ሲመለሱ፣ ከአቶ አክሊሉ ሀብተወልድ የተላከ የግል ማስታወሻ ደረሳቸው።

ለክቡር ወዳጄ ብላታ ኤፍሬም፣

የጻፉልኝ ደብዳቤ ደርሶኝ፣ በእኔ በኩል የተቻለውን ሁሉ በማድረግ የተጨነቁበት ጉዳይ እንዲወገድ ተሳክቶልኛል።

እርስዎ በጣም የተጨነቁበትና ጤናም እስከማጣት ያደረስዎት፣ ለጃንሆይ ውሸት ተናግሬያለሁ ብለው ነው። መጀመሪያ እርስዎ ለጃንሆይ የላኳቸውን ማስታወሻዎች ሁሉ እኔ እንደአየኋቸው፣ በምን ጉዳይ ላይ ውሸት እንደተናገሩ መረዳት አልቻልኩም። የተለየ የምርምር ጥናት ማድረግም አስፈላጊ አልመሰለኝም። የሆነ ሆኖ አንድ ነገር አጥብቄ ላሳስብዎት እፈልጋለሁ። " ... በዚህ በዘመናዊው ዓለም፣ አንድ ጥሩ ዲፕሎማት ለአገሩ ጥቅምና ክብር ሲል፣ መዋሸት ይችላል ... " እርስዎም ዋሽቻለሁ የሚሉት ነገር ካለ፣ የዋሹት ለምንወዳት ኢትዮጵያ ነው በማለት መጨነቁንና መታመሙን ማቆም አለብዎት። በእኔ በኩል የዚህ የጃንሆይና የሩዝቬልት ተገናኝቶ መነጋገር ጉዳይ፣ አሁን ባለንበት የጦርነት ዘመን ለመፈጸም በጣም አስቸጋሪ ስለሆነ፣ ሰላም እስኪመለስ ድረስ ብንጠብቅ ይሻላል በማለት ጸሐፊ ትዕዛዝ ባሉበት ለጃንሆይ በሰፊው አስረድቼ፣ ጃንሆይም ተስማምተውልኝ ነበር። እንደ አጋጣሚ እኔ ከጃንሆይ ጋር ከተነጋገርኩ በኋላ፣ የአሜሪካው ሚኒስትር አስቸኳይ ቀጠሮ ጠይቆ ከቤተመንግሥቱ መጣ። እኔም እዚያው እንድገኝ ጃንሆይ አዘዙ። የአሜሪካው ሚኒስትርም፣ የፕሬዚዳንት ሩዝቬልትና የጃንሆይ ግንኙነት ጦርነቱ ጋብ ሲል በያዝነው ዓመት መጨረሻ ላይ ወይም በመጭው ዓመት መጀመሪያ ላይ እንደሚከናወን ከመንግሥቱ የተላከውን መልዕክት አቀረበ። ጃንሆይም አመስግነው አሰናበቱት። በመሠረቱ፣ የዚህ የዓለም ጦርነት ሳይቃለል ለጃንሆይ ጉዞ የሚመች ስላልሆነ፣ ጥቂት ጊዜ እንዲቆይ መደረጉ በጣም ጥሩ ነው። እንግዲህ፣ እርስዎም

ሰላም ሊያገኙ ይገባል። አሜሪካኖቹ የሚመቹውን ጊዜ መርጠው እስከሚያስታውቁን ድረስ፣ በእርስዎ በኩል የተለየ ጥረት ማድረግ አያስፈልግም።

በዚህ አጋጣሚ ስለ አቶ ጌታሁን ተሰማ ላስረዳዎ የምፈልገው አንድ ነገር አለ። ይህ ሰው አምስቱን ዓመት በአርበኝነት ለአገሩ ነፃነት የተሰቃየ ነው። ነፃነት በተመለሰ ዕለት መጀመሪያ የጽሕፈት፣ ቀጥሎ የአገር ግዛት ዋና ዲሬክተር ሆኖ ከሠራ በኋላ፣ የዋሽንግተን ሌጋሲዮናችን አንደኛ ጸሐፊ ሆኖ መመደቡ በጣም የሚያሳዝን ነው። እኛ ጓደኞቹ መኰንን ደስታ፣ ይልማ ዴሬሣና እኔ የካቢኔ አባሎች ስንሆን፣ ጌታሁን በችሎታውም ሆነ በአገር ፍቅሩ ቢያንስ ከእኛ ደረጃ መለየት አልነበረበትም። በዚህ በእሱ ላይ በደረሰው በደል ማንን ኃላፊ አድርጌ እንደማወግዝ ስም አልጠራም። እርስዎ ግን አቶ ጌታሁን የሰጠኝ አጉል ምክር በሚል መንፈስ ቅሬታ እንደአሳደሩበት ጠቅሰውልኛል። እኔ ጌታሁንን የማውቀው፣ ከልጅነት ጀምሮ በተማሪ ቤት ነው። ተንኮል ምን እንደሆነ አያውቅም። ግን በጣም ጠንካራና ልበ ሙሉ የሆነ ጨዋ ሰው ነው። ለእርስዎም የሰጠውን ምክር ከደብዳቤዎ እንደተረዳሁት፣ ትክክለኛውን የዲፕሎማሲ አሠራር ነው። ስለዚህ፣ በእርስዎ በኩል ከጌታሁን ጋር ተግባብቶና ተቀራርቦ መሥራት እንጂ፣ መለያየቱ ወይም መራራቁ የሚበጅ አይሆንም። ይህንንም ገልጬ የምነግርዎት፣ ወዳጅነትዎን ስለምፈልገውና ስለማምነው ነው።

በሰላም ይግጠመን
ፊርማ አክሊሉ ሀብተወልድ

ብላታ ኤፍሬም ከአቶ አክሊሉ በደረሳቸው ደብዳቤ በጣም ተደሰቱ። ወዲያውም ወደ አንደኛው ጸሐፊ ቢሮ ሄደው፣ " ... እባክህ ወዳጄ ባደረግኩት ስሕተት ይቅርታ አድርግልኝ ..." ብለው ለመኗቸው። አቶ ጌታሁንም፣ " ... መጀመሪያ እርስዎ የፈጸሙት ስሕተት እኔም ያላወቅኩት የትኛው ኖርዋል? ... " ብለው ጠየቁ። ብላታ ኤፍሬም ጥፋቴን የማውቀው እኔ ብቻ ስለሆንኩ፣ የምጠይቅህን "ይቅርታ" ብቻ አድርግልኝ ብለው ልመናቸውን አጠነከሩ። አቶ ጌታሁንም የተደረገውን ስሕተት ካልነገሩኝ ይቅርታ የሚባለውን ጥያቄ አልቀበልም በማለት በሐሳባቸው ጸኑ። ከብዙ ክርክር በኋላ፣ ብላታ ኤፍሬም በአቶ ጌታሁን ላይ አለአግባብ ጥርጣሬ አድሮባቸው እንደነበረ መናዘዝ ግዴታ ሆነባቸው። በመጨረሻው አቶ ጌታሁን ይቅርታ አድርገውላቸው፣ ከእንግዲህ ወዲህ በመካከላቸው የመልካም መግባባትና የተባብሮ መሥራት መንፈስ እንዲቀጥል ተስማምተው ተለያዩ።

ከዚህ በላይ እንደቀረበው፣ የኢትዮጵያና የዩናይትድ ስቴትስ መሪዎች በአንድ ቦታ ላይ ተገናኝተው ለመነጋገር እንዲችሉ፣ የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ይህንን ያህል ብርቱ ጥረት የሚያደርገው ለምን ጥቅም ነው? ተብሎ በአንባቢዎች ዘንድ ጥያቄ መቅረቡ የማይቀር ነው ብለን እናስባለን። የዚህ መጽሐፍ አዘጋጅ፣ በዚህ ጉዳይ ላይ የረዥም ጊዜ ጥናት አካሂዶ እንደተረዳው፣ ጃንሆይ ሩዝቬልትን ለማግኘት በብዙ የደከሙት፣ ለኢትዮጵያ ነፃነትና መብት አንድ ዓይነት ድጋፍ በመስጠት፣ ከእንግሊዞች ውስብስብ ችግር ያድኑናል ብለው ከልባቸው ስለአመኑበት ነው። በዚህ ምዕራፍ ፲ ላይ እስካሁን የተገለጸው፣ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትና የአሜሪካ ፕሬዚዳንት በአንድ ቦታ ላይ ለመገናኘት እንዲችሉ፣ አዲስ አበባ በገነተ ልዑል ቤተመንግሥትና ዋሽንግተን በኢትዮጵያ ሌጋሲዮን መካከል፣ የተለዋወጡትን የዲፕሎማቲክ ኮሬስፖንዳንሶችና መምሪያዎች ዋና ዋናዎቹን እየለቀመ፣ ደራሲው



ለክቡር ወዳጄ ብላታ ኤፍሬም፤
" ... በዚህ በዘመናዊው ዓለም፤ አንድ ጥሩ ዲፕሎማት ለአገሩ ጥቅምና ክብር ሲል መዋሸት ይችላል
...እርዎም ዋሽቻለሁ የሚሉት ነገር ካለ፤ የዋሸሁት ለኢትዮጵያ አገሬ ነው ብለው መጨነቁንና
መታመሙን ማቆም አለብዎት ... "
አክሊሉ ሀብተወልድ

ለአንባቢዎቹ ያቀረባቸው፤ በጉዳዩ ላይ ምን ያህል እንደታሰበበትና ምን ያህል እንደተደከመበት ትክክለኛውን ሥዕል ለማሳየት ይረዳል ብሎ ነው።

ማንም ሰው እንደሚያውቀው፤ የኢትዮጵያ ሕዝብ ነፃነት ከፋሽስት ይዞታ ከተላቀቀ በኋላ፤ በእንግሊዞች ወጥመድ ምን ያህል እንደተሰቃየና ምን ያህል እንደተንገላታ ባለፉት ምዕራፎች በሰፊው ተነግሯል። እንግሊዞች ኃይላቸውን ተማምነው የጫኑብን የመጀመሪያው የሞግዚት አስተዳደር ውል ተፈጽሞ፤ የሁለተኛው የነፃነት ጮራ የፈነጠቀበት ስምምነት በብዙ ትግል ጸድቆ ቢፈረምም፤ የታላቋ ብሪታንያ የጦር ኃይሎች፤ ኦጋዴንን እና ሪዘርቭድ ኤሪያ የተባለውን ግዛቶቻችንን ይዘው በመቆየታቸው፤ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የኢትዮጵያን ነፃነት የሚያረጋግጥላቸው ሆኖ አላገኙትም።

ገና ከጠዋቱ "አጋር ፍለጋ ወደ አሜሪካ" በማሰብ፤ የመጀመሪያውን የይልማ ዴሬሣን ሚሲዮን ወደ ዋሽንግተን ልከው፤ ፍሬያማ ውጤት ይዞ ከተመለሰላቸው በኋላ፤ እሳቸው ራሳቸው ደግሞ የዓለም ሕዝብ የዴሞክራሲና የነፃነት ታጋይ ተብሎ የሚጠራውን ፕሬዚዳንት ሩዝቬልትን አግኝቶ ለማነጋገርና፤ በአገራችን ላይ ከማያንዣብበው የእንግሊዝ ኃይል፤ ኢትዮጵያን ያላቅቃታል ብለው ተስፋ በማድረግ፤ ሌት ተቀን ሲሠሩ ቆዩ። አሁን በእግዚአብሔር ቸርነት ከአንድ ዓመት ተኩል ብርቱ ጥረት በኋላ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከአሜሪካው ፕሬዚዳንት ጋር ተገናኝተው ለመነጋገር የሚያስችላቸው ዝግጅት እየተፋፋመ ስለመጣ፤ ከዚህ በሚቀጥለው በስምንተኛው (፰ኛ) ምዕራፋችን ላይ የጉዳዩን አፈጻጸም እናቀርባለን።

# ምዕራፍ ፲

## የስዌዝ ካናል ምሥጢራዊ ጉዞ፤ ቀ.ኃ.ሥ ከሩዝቬልት ጋር

የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትና የዩናይትድ ስቴትስ ፕሬዚዳንት፤ በዋሽንግተን ወይም በአንድ ሌላ አማካይ ቦታ ተገናኝተው ለመነጋገር እንዲችሉ፤ ምን ያህል ጥረት ሲደረግ እንደቆየ ባለፈው ምዕራፍ ፱ ላይ በሰፊው ተገልጿል። የእነዚህ የሁለቱ መሪዎች ግንኙነት ጉዳይ ሐሳቡ ከተፀነሰ ከሐያ ወራት በኋላ፤ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት በ "ያልታ" ከተደረገው የሦስቱ የዓለም ታላላቅ መሪዎች* ስብሰባ መልስ፤ በግብፅ ግዛት በስዌዝ ካናል ላይ የካቲት 13 ቀን 1945 ዓ.ም እንዲከናወን ወሰነ።

እ.ኤ.አ እሁድ የካቲት 4 ቀን 1945 ዓ.ም አዲስ አበባ ያለው የአሜሪካ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ጆን ኬኔት ካልድዌል (John Kenneth Caldwell) ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የተላከውን ጥሪ እንዲያቀርብና መልሱን እንዲያገኝ እጅግ አስቸኳይ ትዕዛዝ ደረሰው። ቀኑ እሁድ በመሆኑ፤ ጃንሆይ የሚገኙት በገጠር ማረፊያቸው በቢሾፍቱ ነው ተብሎ ስለተነገረው፤ ሰኞ አዲስ አበባ ከመመለሳቸው በፊት አስቸኳዩን መልዕክት ሊያቀርብላቸው እንደማይችል ተገነዘበ። ሆኖም ንጉሠ ነገሥቱ በጣም የሚፈልጉት ጉዳይ ስለሆነ፤ በቀጥታ ቢሾፍቱ በሚገኘው "ፌርፊልድ" ቤተመንግሥታቸው ልሂድና ራሳቸውን አግኝቼ ጥሪውን ለማቅረብ መሞከር አለብኝ ብሎ ወሰነ። የአሜሪካኑ ሚኒስትር ከአዲስ አበባ ወደ ቢሾፍቱ ከመጓዙ በፊት፤ አቶ አክሊሉ ሀብተወልድንና አቶ ይልማ ዴሬሣን በስልክ ለማግኘት ሞክሮ አልተሳካለትም። ነገር ግን የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴርን አማካሪ አሜሪካዊውን ሚስተር ስፔንሰርን አግኝቶ፤ የቤተመንግሥቱን ሰዎች ስለምታውቅ ትረዳኛለህ ብሎ ወደ ቢሾፍቱ ይዞት ሄደ። ስፔንሰር ፈረንሣዊኛ የሚናገር በመሆኑ፤ ጃንሆይ ከአሜሪካው ሚኒስትር ጋር ለሚለዋወጡት ሐሳብ አስተርጓሚ በመሆን እረዳለሁ ብሎ አስቦ ነበር።

ሚኒስትር ካልድዌል ቢሾፍቱ ከፌርፊልድ ቤተመንግሥት እንደደረሰ፤ ሻለቃ መርዕድ መንገሻ የግርማዊነታቸው ዋና የእልፍኝ አስከልካይ ተቀብለው የመጣበትን ጉዳይ ከተረዱ በኋላ፤ ወዲያውኑ ከጃንሆይ ጋር አገናኙት። " ... ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ከያልታ ኮንፌራንስ ሲመለሱ፤ በስዌዝ ካናል የግብፅ ግዛት ውስጥ ግሬት ቢተር ሌክ (Great Bitter Lake) በተባለ ቦታ የካቲት 13 ቀን ማለት ከአንድ ሳምንት በኋላ የኢትዮጵያን ንጉሠ ነገሥት ለመቀበል የተከበረ ጥሪያቸውን ልከውልዎታል ... " ሲል ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሩ መልዕክቱን አቀረበ። ጃንሆይ አስተርጓሚ አላስፈለጋቸውም። የአሜሪካኑ ሚኒስትር ያቀረበውን መልዕክት በእንግሊዝኛ ካዳመጡ በኋላ፤ ነገ ሰኞ (5/02/1945) ከእኩለ ቀን በፊት በስድስት ሰዓት መልሱን እንሰጥሃለን ብለው በእንግሊዝኛ ቋንቋ አሰናበቱት።

---

* ሦስቱ የዓለም መሪዎች፤ ሩዝቬልት፤ ስታሊንና ቸርችል ናቸው። ፈረንሣይ አልተጋበዘችም።

ሚኒስትር ካልድዌል በጣም ተገረሙ። ይኸውም፣ ፩ኛ፣ ጃንሆይ ያለ አስተርጓሚ በእንግሊዝኛ መናገራቸው ሲሆን፣ ፪ኛ ደግሞ በጣም ሲያስቡበት የቆዩት የሩዝቬልት ቀጠሮ እንዲህ በድንገት ከተፍ ሲልላቸው፣ የተለየ ደስታ ካለማሳየታቸው በላይ፣ ጥሪውን ወዲያውኑ ተቀብያለሁ ለማለት አለመፈለጋቸው ነበር። ካልድዌል በዚሁ ዕለት ማታ ከቢሾፍቱ አዲስ አበባ ከተመለሰ በኋላ፣ አቶ አክሊሉ ሀብተወልድን በስልክ አግኝቶ፣ በፌርፊልድ ቤተመንግሥት የደረሰውን ሁኔታ በመገረም ስሜት አጫወታቸው። የጃንሆይ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር አስተያየታቸውን እንደሚከተለው ገለጹለት።

1. ከሁሉ በፊት አንተ የታላቁ ወዳጃቸው የፕሬዚዳንት ሩዝቬልት እንደራሴ በመሆንህ ነው እንጂ፣ ሌላ ዲፕሎማት ያለ ቀጠሮ በገጠር ማረፊያቸው ድረስ ሄዶ በጥቂት ደቂቃዎች ውስጥ ሊያገኛቸው አይችልም ነበር።

2. ጃንሆይ አንተን ሲቀበሉ፣ አስተርጓሚ አልፈልግም ብለው ብቻቸውን በእንግሊዝኛ ቋንቋ ያነጋገሩህ፣ የፕሬዚዳንት ሩዝቬልትን ጥሪ በብርቱ ምሥጢር ለመያዝ አስበው መሆኑን እንድትገነዘበው ያስፈልጋል።

3. መልሱን ወዲያውኑ ሳይሆን በማግሥቱ ጠዋት እንደሚደርስህ የነገሩህ፣ አዲስ አበባ ተመልሰው ንጉሣዊ ቤተሰቦቻቸውንና በጉዳዩ አግባብ ያላቸውን ሚኒስትሮቻቸውን በወግ ለማማከር አስበው እንጂ፣ መልሱ ምንም ጥያቄ የማይቀርብበት "እሺ" መሆኑ የተረጋገጠ ነው አሉት።

ሚስተር ካልድዌል ከአቶ አክሊሉ እንደተነገረው፣ **ጃንሆይ በማግሥቱ ሰኞ የካቲት 5 ቀን 1945 ዓ.ም እኩለ ቀን ስድስት ሰዓት ላይ በገነተ ልዑል ቤተመንግሥታቸው ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት የተላከላቸውን ጥሪ መቀበላቸውን ለአሜሪካው ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር አስታወቁት።**

ከላይ እንደተጠቀሰው የሩዝቬልትን ጥሪ ጃንሆይ ተቀብለው መልስ ከሰጡበት ከሰኞ የካቲት 5 ቀን ጀምሮ ወደ ስዌዝ ካናል እስከተጓዙበት ሰኞ የካቲት 12 ቀን 1945 ዓ.ም ድረስ ባለው በአንድ ሳምንት ጊዜ ውስጥ፣ የሚያስፈልገው ዝግጅት በብርቱ ምሥጢር ሲከናወን ቆየ።

1ኛ/ ንጉሠ ነገሥቱ፤
- ግርማዊት እቴጌ መነን፣
- ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ፣
- ብፁዕ እጨጌ ገብረጊዮርጊስ (ኋላ አቡነ ባስልዮስ)፣
- ቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው (ኋላ ራስ ቢትወደድ)፣
- አባ ሐና ጅማ

ባሉበት ልዩ ስብሰባ በማድረግ፣ ከዚህ ቀደም ጃንሆይ ወደ ማይጨው ዘመቻ ሲሔዱ፣ (በኅዳር 1928 ዓ.ም) ያደረጉትን ኑዛዜ መሠረት በማድረግ፣ የሚሻሻለው ተሻሽሎ፣ በአዲሱና አሁን ባለው ሁኔታ እንዲዘጋጅ መምሪያ ሰጡ።

2ኛ/ ቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው ጠቅላይ ሚኒስትር፤
- ራስ አበበ አረጋይ የጦር ሚኒስትር፣

- ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ የጽሕፈትና የአገር ግዛት ሚኒስትር፣
- አቶ መኰንን ሀብተወልድ የእርሻ፣ የንግድና ኢንዱስትሪ ሚኒስትር፣
- አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ የውጭ ጉዳይ ም/ሚኒስትር፣
- አቶ ይልማ ዴሬሣ የገንዘብ ም/ሚኒስትር፣
- አቶ አካለወርቅ ሀብተወልድ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር እና ቃለ ጉባኤ ያዥ፤

በተገኙበት በአምሳለ ገነት ጽሕፈት ቤታቸው ጃንሆይ ባደረጉት ስብሰባ፤ የአሜሪካው መሪ ፕሬዚዳንት ፍራንክለን ሩዝቬልት፤ በስዌዝ ካናል ለመገናኘት ያደረጉላቸውን ጥሪ መቀበላቸውን አስታወቁ።

በስብሰባው ላይ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ፤ ግርማዊ ንጉሠ ነገሥት ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጋር የሚነጋገሩባቸውን ዋና ዋና ጉዳዮች፤ ፩ኛ፤ በሚሞራንደም የሚቀርቡትን፤ ፪ኛ፤ በቃል ጃንሆይና ፕሬዚዳንቱ ለብቻቸው ሆነው የሚነጋገሩባቸውን ምሥጢርነት ያላቸውን ጉዳዮች እየለየ፤ በአቶ አክሊሉ ሀብተወልድ የሚመራው የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር አዘጋጅቶ እንዲያቀርብ በአሳሰቡት መሠረት፤ <u>ንጉሠ ነገሥቱ እንዲፈጸም ትዕዛዝ ሰጡ</u>። ሌላው በዚህ በአምሳለ ገነት በተደረገው ጉባኤ ላይ በጣም አከራካሪ ሆኖ የነበረው፤ የግርማዊነታቸው በፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ተጠርቶ ወደ ስዌዝ ካናል መሔድ አዲስ አበባ ላለው የታላቋ ብሪታንያ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ይገለጽለት? ወይስ ጉዳዩ በምሥጢር ተይዞ ይቆይ? በሚለው ሐሳብ ላይ ነበር።

የውጭ ጉዳይ ኃላፊው አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ የሚከተለውን አስረዱ።

" ... ጃንሆይ እንደሚያውቁት የፕሬዚዳንት ሩዝቬልትና የግርማዊነትዎ በስዌዝ ካናል ላይ መገናኘት፤ እስከ መጨረሻው ሰዓት በብርቱ ምሥጢር ተይዞ እንዲቆይ፤ በአሜሪካኖቹና በእኛ መካከል ሙሉ ስምምነት ተደርጉበታል። ነገር ግን በውጭ ጉዳይ ኃላፊነቴ የሚታየኝን አንድ ችግር ለግርማዊነትዎ ማመልከት እንዲፈቀድልኝ እለምናለሁ። ይህም "ችግር" ብዬ የምጠራው፤ በግርማዊነትዎ መንግሥት ዘንድ የታላቋ ብሪታንያ እንደራሴ ሆኖ አዲስ አበባ የሚኖረው ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር፤ ይህን ጉዳይ ማወቅ አለበት ወይም የለበትም ከሚለው ከሁለት ሐሳብ መካከል አንዱ እንዲወሰን ነው። እኔ እንደ ውጭ ጉዳይ ኃላፊነቴ እንደሚመስለኝ፤ ይህ ጉዳይ ለእንግሊዙ ሚኒስትር ተደብቆ እስከመጨረሻው ቀን ድረስ ማቆየት የሚጠቅም አይመስለኝም። ይልቁንም፤ እኔ እንደምጠረጥረው የአሜሪካኑ ሚኒስትር ሚስተር ካልድዌል እስካሁን ለእንግሊዙ ለሚስተር ሐው ምሥጢሩን ሳያካፍለው አልቀረም። ከዚህም በላይ፤ ምንም የተለየ መረጃ ባይኖረኝም፤ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልትም ከያልታ ሲነሣ ለጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል በስዌዝ ካናል ላይ በአካባቢው ከሚገኙት ከአንዳንድ መሪዎች ጋር የሚነጋገር መሆኑን ሳይገልጽለት አልቀረም ብዬ አምናለሁ። ምክንያቱም ለዓለም ሰላምና ለጋራ ጥቅማቸው እየተረዳዱ በቅርብ የሚሠሩ ታላላቅ መሪዎች ማንኛውንም እንቅስቃሴያቸውን ተገላልጠው መነጋገራቸው የማይጠረጠር ስለሆነ ነው። በእኔ በኩል በዚህ ጉዳይ ላይ በጣም ካሰብኩበት በኋላ፤ የእንግሊዙን ሚኒስትር በወዳጅነት ጃንሆይ ከቤተመንግሥትዎ ጠርተው፤ በቅርቡ ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጋር በስዌዝ ካናል ለመገናኘት ጥሪ የደረስዎ መሆኑን ቢገልጹለት፤ ያለጥርጥር በመልካም መንፈስ ይቀበለዋል። ነገር ግን ከግርማዊነትዎ በኩል ምንም ሳይነገረው

ቢቀርና በመጨረሻው ደቂቃ እንደማንም ሰው ከውጭ ቢሰማው፤ በእኛ ላይ ቅያሜውን እንደሚያጠነክርና፤ በሚቻለው ሁሉ እኛን የሚጉዳ ነገር ከመሥራት አይመለስም ብዬ እሠጋለሁ። ስለዚህ፤ ቀደም ብዬ እንዳሳሰብኩት ቢቻል ጃንሆይ ቢያነጋግሩት፤ ይህ ይበዛል ከተባለም፤ እኔ በውጭ ጉዳይ ኃላፊነቴ ጠርቼ እንዳነጋግረው የግርማዊነትዎን መልካም ፈቃድ እለምናለሁ ... "

ጃንሆይ ከውጭ ጉዳይ ም/ሚኒስትሩ የቀረበውን ካዳመጡ በኋላ፤ የስብሰባው ተካፋዮች የሆኑትን ሁሉ አስተያየታቸውን እንዲሰጡ አዘዙ።

- ክቡር ቢትወደድ መኰንን ጠቅላይ ሚኒስትር፤
- ክቡር ራስ አበበ አረጋይ የጦር ሚኒስትር፤
- ክቡር አቶ መኰንን ሀብተወልድ የእርሻ፣ የንግድና የኢንዱስትሪ ሚኒስትር፤

ባቀረቡት ተመሣሣይ አስተያየት፤ " ... <u>የጃንሆይ ወደ ስዌዝ ካናል ጉዞና ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጋር መገናኘት፤ በብርቱ ምሥጢር ተይዞ እንዲቆይ የጠየቁት አሜሪካኖቹ ስለሆኑ፤ ለእንግሊዙ ወኪል ለመንገርም ለመደበቅም ኃላፊነቱ የአሜሪካው ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ፋንታ ነው። እኛ በዚህ በኩል መስጋትም ማሰብም የለብንም</u> ... " አሉ።

ከታላላቆቹ ቀጥሎ አቶ ይልማ ዴሬሣ የገንዘብ ም/ሚኒስትር የሚከተለውን ሐሳብ አቀረቡ። " ... የጃንሆይ ወደ ስዌዝ ካናል ለመጓዝና ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጋር ለመገናኘት የሚደረገው ዝግጅት፤ ለታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የተደበቀ ምሥጢር መሆን አይችልም። አቶ አክሊሉ ደህና አድርጉ አስረድቷል። <u>ይህን ጉዳይ ጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት እንደሰማ፤ የአዲስ አበባው የእንግሊዝ ሚኒስትርም ከጓደኛው ከአሜሪካው ሚኒስትር እንደተነገረው ጥርጥር የለውም።</u> ስለዚህ፤ እኛ ብንደብቀው በእኛ ላይ ቅሬታውንና ቅያሜውን ከማጠንከሩ በስተቀር፤ ምሥጢርነቱን አያድነውም። ምሥጢር መሆኑን ገልጠን ብንነግረው ግን፤ አልደበቁኝም ብሎ መልካም አስተያየት ያድርበታል እንጂ፤ ምንም ዓይነት ቅሬታ ሊሰማው አይችልም። ስለዚህ አቶ አክሊሉ እንደአሳሰበው፤ <u>ሲሆን ጃንሆይ ጠርተው ቢያነጋግሩት፤ ሳይሆን ደግሞ የውጭ ጉዳይ ኃላፊው ተቀብሎ ቢገልጽለት የተገባ ነው ብዬ ሐሳቤን አቀርባለሁ</u> ... "

## <u>የጃንሆይ ውሣኔ፤</u>

" ... ብዙ ጊዜ እየተደጋገመ እንዳየነው፤ እኛ በምናደርገው ስብሰባ ላይ ይልማ ዴሬሣና አክሊሉ ሀብተወልድ እየተደጋገፋችሁ ታላላቆቻችሁ የሚያቀርቡትን ሐሳብ መቃወምና የራሳችሁን ትልቅ አስመስሎ መናገር፤ እንደ መልካም ሥራ አድርጋችሁ የምትቆጥሩት ይመስላል። እርግጥ ነው፤ አንድ ጉዳይ በጉባኤ ቀርቦ ሲጠና፤ እያንዳንዱ ሰው የተለያየ ሐሳብ ሊኖረው ይችላል። ይህም የዘመኑ ዴሞክራሲ አሠራር የሚጠይቀው ነው ብለን እንቀበለዋለን። ነገር ግን፤ በየስብሰባው ላይ ሁለትና አንዳንድ ጊዜም ሦስት ሰዎች፤ በአንድ ጉዳይ ላይ ሲደግፉም በአንድነት፤ ሲቃወሙም በአንድነት እየሆኑ የምናያቸው፤ ወደ ፓርቲ ያዘነበለ አሠራር ነው እንጂ፤ የዴሞክራሲን ወግ የተከተለ ነው ማለት አይቻልም። ይህንንም እስከመናገር ያደረሰን፤ አክሊሉና ይልማ በአንድ ድምፅ እየደጋገማችሁ የምትናገሩት እያስገረመን ነው። ሁለታችሁም ልብ ብላችሁ ብትመለከቱት፤ <u>አንድ</u>



ጃንሆይ ወደ ስዌዝ ካናል ከመሄዳቸው አንድ ቀን በፊት፤ በገነተ ልዑል ቤተመንግሥት በተደረገው የእራት ግብዣ ላይ፤ የአሜሪካንን ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ሲያነጋግሩ፤



ጃንሆይ ስዌዝ ካናል ሲደርሱ፤ የአሜሪካ ባለሥልጣኖች ሲቀበሏቸው፤

ወዳጅ መንግሥት በብርቱ ምሥጢር ይያዝልን ብሎ ያቀረበልንን ጉዳይ፤ ከራሳችን አሳልፈን ለውጭ መንግሥት እንደራሴ ማካፈል ጨርሶ ተገቢ አለመሆኑን ለመረዳት ትቸገራላችሁ ብለን አናስብም። አክሊሉና ይልማ የተናገራችሁት የቃሉ አቀራረብ ካልሆነ በስተቀር፤ ሐሳባችሁ አንድ ዓይነት መሆኑን ተረድተናል። የእኛን ወደ ስዌዝ ካናል መጠራት፤ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ለሚስተር ቸርችል፤ አዲስ አበባ ያለው የአሜሪካው ሚኒስትር ደግሞ ለእንግሊዙ ወኪል፤ እንደሚነግሯቸው እርግጠኞች ነን ብላችኋል። እንደዚህ ይሆናል ካላችሁም፤ ቅድም መኰንን ሀብተወልድ እንደተናገረው፤ አዲስ አበባ ላለው ለእንግሊዙ ሚኒስትር ምሥጢሩን አውጥቶ ለመንገርም ሆነ ወይም ደግሞ አያስፈልግም ብሎ ለመደበቅ፤ ኃላፊነቱ የአሜሪካኖች ስለሆነ፤ እኛን አይመለከተንም ብለን መወሰናችንን እንድታውቁት ይሁን። በዚህ ጉዳይ ላይ ሁላችሁም የሚመስላችሁን ሐሳብ ስትገልጹ፤ ወልደጊዮርጊስ ብቻ ምንም አስተያየት ለማቅረብ አለመፈለጉ ሳይገርመን አልቀረም። ወልደጊዮርጊስ ያልተናገረው፤ ምናልባት ሐሳቡ ወደ አክሊሉና ይልማ አዘንብሎ ይሆናል። ለማናቸውም እኛ በውሳኔያችን ወደ ኋላ አንመለስበትም። በእኛና በመንግሥታችን በኩል ለእንግሊዙ ሚኒስትር የሚነገር ነገር የለም። ይኸ በእኛ በኩል የተቋረጠ ነው። አሁን ወደ ሁለተኛው ጉዳይ እንሻገርና እኛን ተከትለው የሚሔዱትን ሰዎች፤ ወልደጊዮርጊስ ከእኛ ጋር በተነጋገርከው መሠረት ዝርዝሩን አቅርብ!

ጸ.ት.ወ፤ የአሜሪካን ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ለእኔና ለአቶ አክሊሉ እንደነገረን፤ ከጃንሆይ ጋር ሰባት ሰዎች ብቻ ናቸው መሄድ የሚችሉት። እነዚህም፤ በጃንሆይ መልካም ፈቃድ ተከታዮች እንዲሆኑ የታዘዙት፤

1. ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ፣
2. አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ፤ የውጭ ጉዳይ ም/ሚኒስትር
3. አቶ ይልማ ዴሬሣ፤ የገንዘብ ም/ሚኒስትር
4. ሻለቃ መርዕድ መንገሻ፤ የግርማዊነታቸው ዋና የእልፍኝ አስከልካይ
5. ሚስተር ጆን ስፔንሰር፤ የውጭ ጉዳይ አማካሪ
6. ልጅ ከበደ አበበ፤ የግርማዊነታቸው የእልፍኝ አሽከር ናቸው።

ጃንሆይ፤ ይኸው እንደሰማችሁት፤ ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት የሚላክልን ልዩ አውሮፕላንና በስዌዝ ካናልም የተዘጋጀልን ማረፊያ ቤት ከተወሰኑ ሰዎች በላይ መያዝ የማይችል በመሆኑ፤ እኛን ተከትሎ መሔድ የሚገባው ወልደጊዮርጊስም መቅረቱ ግዴታ ሆኖብናል። ሌላው ስለጉዞአችን ፕሮግራም አክሊሉ የምትናገረው የለም ? ...

አክሊሉ፤ ትናንት ከክቡር ጸሐፊ ትዕዛዝ ጋር ሆነን፤ የአሜሪካንን ሚኒስትር አነጋግረነው ነበር። ጃንሆይ ከአዲስ አበባ የሚነሱት፤ ሰኞ የካቲት 12 ቀን ከንጋቱ 12 ሰዓት ላይ ሲሆን፤ በዚሁ ዕለት ስዌዝ ካናል ደርሰው በዚያው አዳር ከሆነ በኋላ፤ ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጋር የሚገናኙት ማክሰኞ የካቲት 13 ቀን ወደ ማታ ነው። ዝርዝሩ ፕሮግራም እንደተጠናቀቀ ሚኒስትሩ ይነግረናል። ጃንሆይ አዲስ አበባ የሚመለሱት ሮብ የካቲት 14 ቀን እንደሚሆን ታውቋል።

አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ የጉዞውን ፕሬግራም በአጭሩ ካስረዱ በኋላ፤ ንጉሠ ነገሥቱ ስብሰባውን ሲዘጉ የሚከተለውን ተናገሩ።

" ... ይኸው እንደሰማችሁት ከብዙ ጊዜ ጀምሮ ሲታሰብበት የቆየው የፕሬዚዳንት ሩዝቬልትና የእኛ ተገናኝቶ መነጋገር፤ የእግዚአብሔር ፈቃዱ በሆነበት ሰዓት ሊፈጸም ተዘጋጅቷል። ሁላችሁም እንደምታውቁት ዛሬ ባለንበት ዘመን ይህች የተጠቃችና የተበደለች አገራችን፤ ለሰላም ሕይወቷና ለሥልጣኔ እድገቷ ከልቡ የሚደግፋት ወዳጅ መንግሥት ያስፈልጋታል። ታላላቆቹ አውሮፓውያኖች ኢትዮጵያን በወዳጅነት እናስባታለን እያሉ በአንዳንድ ዲስኩራቸው ቢያወሷትም፤ የሚያስቧት በኮሎኒ መንፈስ እንጂ፤ ነፃነቷን ለመጠበቅ አይደለም። አሜሪካ ግን ዞሮ ዞሮ ለነፃነታችን ተቀናቃኝ አይሆንም ብለን ስለምናምን፤ ወዳጅነታችንን ለማጠንከርና ድጋፉን ለማግኘት መጣር ይሻለናል ብለን መንገዱን ጀምረናል። መጀመር የሰው ልጆች ልምድ ቢሆንም፤ ፈጻሚው እግዚአብሔር ነው። እግዚአብሔርንም አጥብቀን የምንለምነው፤ አገራችንን ኢትዮጵያን ከወዳጅ ጠላት እንዲሠውራት ነው። ይህንን ያሰብንበትን ጉዳይ ፈጽመን በደህና ስንመለስ፤ ያመረትነውን እንነግራችኋለን። ሁላችሁም በየበኩላችሁ፤ የአገራችንን ደህንነት ለመጠበቅ በምትሠሩት ሁሉ እግዚአብሔር ይርዳችሁ! ... "

ቀደም ሲል በተገለጸው ፕሮግራም መሠረት፤ እ.ኤ.አ ሰኞ የካቲት 12 ቀን 1945 ዓ.ም ከንጋቱ 12 ሰዓት ላይ ንጉሠ ነገሥቱ ከአዲስ አበባ ተነሥተው ስዌዝ ካናል ከደረሱ በኋላ፤ በማግሥቱ ማክሰኞ ከቀትር በላይ በአሥራ አንድ ሰዓት (5.00 p.m) ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት በልዩ መርከባቸው ውስጥ ተቀብለዋቸው አንድ ሰዓት ከአምሳ ደቂቃ አነጋገሯቸው።

## ዩናይትድ ስቴትስና ኢትዮጵያ

በመጀመሪያ የሁለቱም መሪዎች ረዳቶችና መልዕክተኞች በተገኙበት ስብሰባ ላይ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ለፕሬዚዳንት ሩዝቬልት በስድስት ነጥቦች ያቀረቡላቸው የኢትዮጵያ ጉዳዮች የሚከተሉት ነበሩ።

### ሀ/ የኤርትራ ወደ ኢትዮጵያ መመለስ፤

እ.ኤ.አ በ1885 ዓ.ም፤ ኮሎኒያሊስት ጣልያን በመጀመሪያ የአሰብን፤ ቀጥሎም የምፅዋን ወደቦቻችንን በጦር ኃይል ከያዘ በኋላ፤ ቀስ በቀስ እየተጓዘ እስከ መረብ ወንዝ ድረስ ያሉትን የኢትዮጵያን አውራጃዎች፤ "ኤርትራ" ብሎ በመሰየም፤ ቅኝ ግዛቱ አድርጐ መጠቅለሉን ታሪክ በትክክል ያረጋግጣል። ኮሎኒያሊስት ጣልያን እነዚህን የኢትዮጵያ ግዛቶች "ኤርትራ" ብሎ በመሰየም ከመያዙ በፊት፤ በኢትዮጵያ ነገሥታቶች አስተዳደር፤ "መረብ ምላሽ" ወይም "ምድረ ሐማሴን" እየተባሉ የሚጠሩ ነበሩ። ከክርስቶስ ልደት በፊት በመጀመሪያውና በሁለተኛው ሺህ ዓመታት ውስጥ፤ የካምና የሴም ነገዶች በቀይ ባሕር በኩል እየተጓዙ ወደ አገራችን ሲመጡ፤ ኢትዮጵያ የተቀበለቻቸው በዚሁ የጣልያን ኮሎኒያሊስት "ኤርትራ" ብሎ በሰየመው መሬት ላይ ነው።

የጥንታዊት ኢትዮጵያ መናገሻ ከተማ በነበረው በአክሱምና በአካባቢው የተገኙት የታሪክ ቅርሶችና ሐውልቶች፤ የአገራችንን የኢትዮጵያን መሠረታዊ ሥልጣኔ የሚያስረዱ መሆናቸው፤ በዛሬዎቹ የታሪክ ተመራማሪዎች ስለተረጋገጠ፤ በመረብ ምላሽ ወይም በምድረ ሐማሴን የኖሩት ሕዝቦች፤ ለኢትዮጵያዊነታቸው የተለየ ማስረጃ ማቅረብ አያስፈልግም። ኮሎኒያሊስት ጣልያንም በመጀመሪያ አሰብን

ይዞ፤ ቀጥሎም በምዕዋ በኩል ጦር አዘጋጅቶ ይህንን "ኤርትራ" ብሎ የሰየመውን አገር ቅኝ ግዛቱ አድርጐ መያዙን አልካደም።

ዛሬ በአለንበት ዘመን፤ የሕዝቦች ነፃነትና መብት እንዲጠበቅ ብዙ ጥረት የሚደረግበት ስለሆነ፤ የኢትዮጵያ አካል የሆነችው ኤርትራ ወደ እናት አገሯ እንድትመለስ፤ ኤርትራውያኖችና ኢትዮጵያውያኖች በአንድነት ተሰልፈው ትክክለኛውን የዓለም ፍርድ ስለጠየቁ፤ በክቡርነትዎ የሚመራው የዩናይትድ ስቴትስ መንግሥት ድጋፉን እንዲለግሳቸው እጥብቀው ይለምናሉ። ኤርትራ ወደ ጥንታዊ አገሯ ወደ ኢትዮጵያ እንድትመለስ የምናደርገውን ጥረት፤ አንዳንድ አገሮች ጥያቄያችን የተመሠረተው የባሕር በር ለማግኘትና የኤኮኖሚ ጥቅም ለማግኘት ነው የሚል አስተያየት ሲሰጡ ይታያሉ። ይህ ትክክለኛ የሆነ አመለካከት አለመሆኑን ማስገንዘብ እንፈልጋለን። ኢትዮጵያ በዙሪያዋ ከሚገኙት የጥንት ግዛቶቿ ውስጥ ካሉት የባሕር በሮች አንደኛው እንዲሰጣት ለመጠየቅ፤ ዛሬ ያለችበት ሁኔታና ጊዜው ይፈቅድላታል። ነገር ግን፤ የኤርትራን ወደ እናት አገሯ መመለስ የንጉሠ ነገሥት መንግሥታችን በሚቻለው ሁሉ የሚደክመው፤ በኮሎኒያሊስቶች የፈረሰብንን ታሪክ እቦታው ለመመለስና የኤርትራውያንንና የኢትዮጵያውያንን ብርቱ ፍላጐት ለመፈጸም በማሰብ እንጂ፤ በኤኮኖሚ ጥቅም ላይ የተመሠረተ ጥያቄ አለመሆኑ እንዲታወቅልን እናመለክታለን።

## ለ/ <u>ከጂቡቲ እስከ አዲስ አበባ ያለውን የምድር ባቡር ኩባንያ ኢትዮጵያ እንድትረከብ፤</u>

እ.ኤ.አ 1908 ዓ.ም በጥርና በመጋቢት ወራቶች በኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትና በፈረንሣይ ሬፑብሊክ መንግሥታት መካከል ስምምነት ተደርጐ፤ ከጂቡቲ እስከ አዲስ አበባ የተዘረጋው የምድር ባቡር መስመር፤ <u>"የኢትዮጵያና የፈረንሣይ የምድር ባቡር ኩባንያ"</u> ተብሎ እየተጠራ ከሁለቱ አገሮች በተውጣጡ የቦርድ አባሎች ሲመራ የቆየ ነው።

ስለ ባቡሩ መስመር ሥራ አመራር በሁለቱ አገሮች ማለት በኢትዮጵያና በፈረንሣይ መካከል በተደረገው ስምምነት በአሥራ ስምንተኛው አንቀጽ ላይ የተደነገገው፤ " <u>... በጦርነት ሰዓት የባቡሩ መስመር ለኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መንግሥት ሙሉ አገልግሎት እንዲሰጥ ይመደባል ...</u> " የሚል ነው። ነገር ግን የሙሶሊኒ መንግሥት በኢትዮጵያ ላይ ጦርነት ባነሳ ጊዜ፤ የፈረንሣይ መንግሥት ስምምነቱን በመጣስ በባቡሩ መስመር ላይ ኢትዮጵያ የሚያስፈልጋትን አገልግሎት እንዳታገኝ ጂቡቲ ላይ አግዶ ያዘው። የፈረንሣይ ክህደት በዚህ ብቻ አልቆመም። ኢትዮጵያ ለነፃነቷ መከላከያ ከአውሮፓ አገሮች በገንዘቧ የገዛቻቸው የጦር መሣሪያዎች ጂቡቲ ሲደርሱ፤ የፈረንሣይ ባለሥልጣኖች ወደ አዲስ አበባ እንዳይሣፈሩ ካደረጉ በኋላ፤ የፋሽስት ጦር ኢትዮጵያን መያዙ ሲረጋገጥ፤ መሣሪያዎቹን እስከ ድሬዳዋ ልከው ለሙሶሊኒ መንግሥት ኃላፊዎች አስረከቡ።

የፈረንሣይ መንግሥት ኢትዮጵያ የገዛቻቸውን የጦር መሣሪያዎች በግፍ ይዞ ለፋሽስት ባያስረክብ ኖሮ፤ የኢትዮጵያ የመከላከያ ኃይል ጠላትን ለብዙ ጊዜ መመከት ብቻ ሳይሆን፤ እንደ አድዋው ጊዜ ድልን የመቀዳጀትም ተስፋ ይኖረው እንደነበረ የሚገምቱ ብዙዎች ናቸው። የሚያስገርመው፤ የፈረንሣይና የፋሽስት መንግሥት ፍቅራቸው ሊዘልቅ አለመቻሉ ነው። አዛዡ አዶልፍ ሒትለር ስለሆነ፤ የናዚ ጦር ፈረንሣይን በሰሜን ግዛቷ በኩል ገብቶ ካደቀቃትና ከወረራት በኋላ፤ የሙሶሊኒ የፋሽስት ኃይል ደግሞ፤ በደቡብ ግዛቷ ዘልቆ ያዛት። የፋሽስት ጦር

የፈረንሣይን ደቡብ ግዛቶችና እንዲሁም የፈረንሣይ ቅኝዎች የሆኑትን አንዳንዶቹን የሰሜን አፍሪካ አገሮች ወደ ፋሽስት አስተዳደር ለማዛወር እርምጃ ከወሰደ በኋላ፤ ከጂቡቲ እስከ አዲስ አበባ ያለውን የባቡር መስመር ወርሶ ለፋሽስት አገልግሎት እንዲውል አደረገ።

እ.ኤ.አ በግንቦት 1941 ዓ.ም የታላቋ ብሪታንያ ጦር፤ የአርበኞቻችንን ድጋፍ ይዞ ፋሽስትን ከኢትዮጵያ ግዛት ካባረረ በኋላ፤ የባቡሩን መስመር ሥራ ወስዶ ይኸው እስከዛሬ ድረስ ያካሂዳል። ከታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ጋር በረዥሙ ተነጋግረን፤ ከዛሬ ሁለት ወር በፊት በታህሣሥ 1944 ዓ.ም በተፈራረምነው ውል፤ የባቡሩን ኩባንያ ኢትዮጵያ እንድትረከብ ስምምነት አድርገናል።

ከቡርነትዎ እንደሚያውቀው፤ የፈረንሣይ መንግሥት አገሬን በዚያ በክፉ ቀን ከፋሽስት ጋር በመተባበር እጅግ የበደላትና ጥቃት ያደረሰባት በመሆኑ፤ የባቡሩን ኩባንያ ተረክባ ማካሄድ ትክክለኛ መብቷ ነው። ስለዚህም፤ ኢትዮጵያ የዩናይትድ ስቴትስን መንግሥት እርዳታ የምትጠይቀው፤ ከአንድ ከታወቀ አሜሪካዊ የባቡር ድርጅት ጋር በመዋዋል፤ ሥራውን ለማካሄድ እንድትችል ነው።

## ሐ/ የጦር መሣሪያ እርዳታ

ኢትዮጵያ እንኳንስ የውጭ ጠላትን ለመከላከያ ቀርቶ፤ የአገር ውስጡንም ፀጥታ ለማስከበር አንዳች መሣሪያ የላትም። ቀደም ብለን እንደአስረዳነው የፋሽስትን ጠላት ለመመከት፤ ኢትዮጵያ ከአውሮፓ የገዛቻቸውን የጦር መሣሪያዎች የፈረንሣይ መንግሥት ጂቡቲ ላይ ቀምቶ ለጠላታችን አስረከበብን። ጠላታችን ድል ሆኖ ከአገራችን ሲባረር፤ ትቷቸው የሸሸውን የጦር መሣሪያዎች ደግሞ፤ የነፃነት ረዳቶቻችን የሆኑት የታላቋ ብሪታንያ የጦር ባለሥልጣኖች፤ አንድ በአንድ እየለቀሙ ወደ ኬንያና ወደ ሌሎቹም ቅኝ ግዛቶቻቸው አሻገሩአቸው። በተሽከርካሪ ትራንስፖርት ጭነው ለመውሰድ ያቃታቸውንም ከባድ መሣሪያዎች፤ በፈንጂ በማፍረስና በመበታተን ከጥቅም ውጭ እንዲሆኑ አደረጓቸው።

ደጋግመን እንደገለጽነው ኢትዮጵያ በአሁኑ ሰዓት፤ እስኪንስ ነፃነቷን ከውጭ ጠላት ለመመከት ይቅርና፤ በአገር ውስጥ ፀጥታ የሚያደፈርሱትን ሽፍቶችና ወንበዴዎች ለመከላከል የሚያስችሉ መሣሪያዎች የሏትም። ነፃነታችንን ከፋሽስት ለማላቀቅ ረዳቶቻችን ሆነው የመጡልን የታላቋ ብሪታንያ የጦር መሪዎች፤ የፈጸሙብን በደል በአጭሩ ተወስቶ የሚያልቅ አይደለም። ጠላታችን ፋሽስት አገራችንን ለቅቆ ሲሸሽ የተዋቸውን የጦር መሣሪያዎች ብቻ ሳይሆን፤ የተሽከርካሪ ትራንስፖርቶችን፤ የቴሌፎን መገናኛዎችንና፤ የኤሌክትሪክ መብራት ኃይል ሞተሮችን አንድ በአንድ እየሰበሰቡ ወደ ቅኝ ግዛቶቻቸው ወስደውብናል። ዛሬ በአለንበት ሰዓት፤ የፀጥታ አስከባሪዎቻችንን ከአንዱ ግዛት ወደ ሌላው የምናጓጉዝበት የትራንስፖርት አገልግሎት መስጫ የለንም። የቴሌፎን መገናኛ መስመሮች ሁሉ እየተነቀሉ ስለተወሰዱ፤ ከየአውራጃዎቹና ከየጠቅላይ ግዛቶቹ ምንም ዓይነት የመገናኛዎች ድርጅት የለንም።

እነዚህ ሁሉ ችግሮቻችን ታይተው፤ ኢትዮጵያ ግዛቶቿን ከውጭ ጠላት ለመከላከያና ለአገር ውስጥ ፀጥታ ማስከበሪያ የሚያስፈልጓት መሣሪያዎች

በእርዳታና በብድር በሚከፈል ገንዘብ ለማግኘት እንድትችል ለወዳጇ ለዩናይትድ ስቴትስ መንግሥት ታመለክታለች።

መ/ ለተባበሩት መንግሥታት መሠረታዊ ቻርት፤ ረቂቁን እንዲያዘጋጅ በሚመረጠው ኮሚቴ፤ ኢትዮጵያ አባል እንድትሆንና በቀድሞው ሊግ ኦፍ ኔሽን የደረሰባትን ኢክስፔሪያንስ ተመርኩዛ ለመጭው የዓለም ሰላም ጥንካሬ የሚቻላትን ሁሉ እንድታበረክት፤ የክቡርነትዎን መልካም ድጋፍ ትጠይቃለች።

ሠ/ በሁለተኛው የዓለም ጦርነት ፍጻሜ በሚደረገው የሰላም ጉባኤ ላይ፤ የኢትዮጵያ ተካፋይነት እንዳይረሣ በቅድሚያ እናሳስባለን። ክቡርነትዎ እንደሚያውቀው፤ ኢትዮጵያ የመጀመሪያዋ በአክሲስ አገሮች የተጠቃችና ነፃነትንም በመቀዳጀት የመጀመሪያዋ ስለሆነች፤ ከዚህ ለሰላም መሥራች ከሆነው የዓለም ጉባኤ መለየት የለባትም ብለን እናስባለን።

ረ/ ኦጋዴንና ሪዘርቭድ ኤሪያ፤ የተባሉትን የኢትዮጵያን ግዛቶች፤ በዚህ በሁለተኛው የዓለም ጦርነት ሰበብ የታላቁ ብሪታንያ መንግሥት የጦር ኃይሎቹን አስፍሮባቸዋል። በእኛ አስተያየት አሁን በሩቅ ምሥራቅ በመካሔድ ላይ ላለው የዓለም ጦርነት፤ የተያዘው ግዛታችን አስፈላጊነቱን ባናምንበትም፤ ከታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ጋር ሰላምን በመፈለግ እስከ መጭው ሁለት ዓመት ድረስ ይዞታው እንዲቆይ ስምምነቱን ፈርመንለታል። ይሁን እንጂ፤ እኛን ሥጋት ላይ የጣለን "Sinclair Oil" ከተባለው የአሜሪካ ኩባንያ ጋር በኦጋዴን ግዛታችን ላይ ስለ ነዳጅ ዘይት ፍለጋ ያደረግነው ስምምነት፤ በእንግሊዞች ምክንያት እንዳይቋረጥብን ነው። "Sinclair Oil" በሚያደርገው ጥረት የሚገኘው ውጤት የጋራ ጥቅማችን ስለሆነ፤ የአሜሪካ መንግሥት ማበረታቻ እንዲሰጥልን እናሳስባለን።

## የሁለቱ መሪዎች የግል ውይይት፤

ፕሬዚዳንት ሩዝቬልትና ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ረዳቶቻቸውንና ተከታዮቻቸውን ይዘው ለአንድ ሰዓት ተኩል በይፋ ከተነጋገሩ በኋላ፤ ለመጨረሻዎቹ አሥራ አምስት ደቂቃዎች ሁለቱ መሪዎች ብቻቸውን ሆነው **በፈረንሣዊኛ ቋንቋ ተወያይተዋል።** ይህ በግልና በቆይታ የተደረጉት ንግግሮች በምን ጉዳዮች ላይ እንደሆኑ ከሁለቱም መሪዎች በኩል መግለጫዎች አልተሰጡም።

ከብዙ ዓመታት በኋላ፤ ክቡር ጸሐፊ ትዕዛዝ አክሊሉ ሀብተወልድ የቀ.ኃ.ሥ ጠቅላይ ሚኒስትር፤ ለዚህ መጽሐፍ ደራሲ የነገሩት የሚከተለውን ነበር። " ... ጃንሆይና ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት በጃንሆይ ጠያቂነት ማንም ሰው አጠገባቸው ሳይኖር በግል የተነጋገሩት፤ እንግሊዞች በኢትዮጵያ ላይ ስለሚፈጽሙት በደል መሆኑን ሁላችንም እናውቅ ነበር። ይኸንንም የሚነጋገሩበትን ጉዳይ፤ ጃንሆይ በሚገባ አጥንተው እንደተዘጋጁበት እናውቃለን። ጃንሆይ ከፕሬዚዳንቱ ጋር ተነጋግረው ከወጡ በኋላ፤ አቶ ይልማ ዴሬሣና እኔ ጠጋ ብለን ጃንሆይ! ውጤቱ ምን ነበር? ብለን ጠየቅናቸው። የሰጡን መልስ በጣም አጭር ነው። " ... ዝርዝሩ **አይጠቀማችሁም። ዋናው ቁም ነገር፤** ከእንግዲህ ወዲህ በማናቸውም መልክ

ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት፤ በመርከባቸው ላይ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ሲቀበሉ፤



ሁለቱ መሪዎች ቀ.ኃ.ሥ እና ሩዝቬልት ለብቻቸው በፈረንሣዊኛ ቋንቋ ሲወያዩ፤

የኢትዮጵያን ነፃነት የሚደፍር እንደማይኖር እርግጠኛ መሆን አለብዎት ! ብለውኛል ... " አሉን።

ከዚያን ጊዜ ጀምሮ የጃንሆይ ሞራል በጣም ከፍ ብሎ፤ አልፎ አልፎ እንግሊዞች የሚያሳዩትንም የበላይነት መንፈስ የማይቀበሉት መሆናቸውን በግልጽ ያሳዩ ነበር።

ደራሲው - እንግዲያውስ ይህ የስዌዝ ካናል ምሥጢራዊ ጉዞና ንግግር፤ ለኢትዮጵያ ትልቅ ድጋፍ አስገኝቷል ማለት አይቻልም ወይ?

ጸ.ት.አ - ለኢትዮጵያ ትልቅ ድጋፍ ማስገኘቱ ጥያቄ የሚቀርብበት አይደለም። የጃንሆይም ሞራል በእንግሊዞች ላይ ተጠናክሮ መታየቱ፤ ከዚሁ ከስዌዝ ካናል ንግግር በኋላ ነው። ታሪኩን ከተከታተልከው፤ ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጋር ተገናኝቶ ለመነጋገር፤ ጃንሆይ ወደ ሁለት ዓመት በሚጠጋ ጊዜ በብዙ የደከሙበትና አጥብቀው ያሰቡበት ጉዳይ ነው። ከካቢኔ ሚኒስትሮቻቸው ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና ከአቶ መኮንን ሀብተወልድ በስተቀር፤ ሌሎቻችን የጃንሆይና የሩዝቬልት ተገናኝቶ መነጋገር የሚጠቅም መሆኑን ብናስብም፤ ጉዳዩ እንዲሳካ ጃንሆይ በተለይ ያደረጉትን ጥረት የሚያህል ሥራ አልሠራንም። ስለዚህ በመጨረሻው የተገኘው ውጤት፤ በጃንሆይ ድካም መሆኑን ማመን አለብን።

ደራሲው - ከጃንሆይና ከሩዝቬልት ንግግር በኋላ፤ ከአሜሪካ መንግሥት ጋር ምን ለማድረግ ታሰበ?

ጸ.ት.አ - የጃንሆይ ሁለተኛው ምኞታቸው፤ ጦርነቱ አልቆ የዓለም ሰላም ሲረጋጋ፤ በሩዝቬልት ዘመን አሜሪካንን በኦፊሲየል ለመጐብኘትና ለኢትዮጵያ የሚጠቅሙ ብዙ እርዳታዎች ለማስገኘት ነበር። ጃንሆይ ገና ከስዌዝ ካናል እንደተመለሱ፤ የገንዘብ ሚኒስትራቸውን ይልማ ዴሬሣን በየቀኑ እየጠሩ ከአሜሪካ መንግሥት ስለምንጠይቀው የልማት እርዳታ ፕላን አዘጋጅተህ አቅርብ እያሉ በጣም ያስጨንቁት ነበር።

ይልማ፤ ለኢትዮጵያ ይበጃል የሚለውን ፕላን አጠናቅቆ ሳይጨርስ፤ ሩዝቬልት ከጃንሆይ ጋር በተዋወቀ በሁለት ወር ጊዜ ውስጥ ሞተ። በዚያን ጊዜ ጃንሆይ አንድ ትልቅ ረዳት አጣን ብለው በጣም አዝነው ነበር። ሆኖም በምትኩ የተሾመው ሔንሪ ትሩማን፤ ሩዝቬልት ለኢትዮጵያ ያሳየውን በጐ መንፈስ ለመቀጠል ሞክሯል። ለምሳሌ፤ በአሜሪካ የኢትዮጵያ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ሆነው የተሾሙትን የራስ ዕምሩን የሹመት ደብዳቤ ሲቀበል ትሩማን ባደረገው ንግግር፤ " ... **እርስዎን የሚያህል ወንድማቸውንና የተከበረ ታሪክ ያለዎትን ትልቅ ሰው፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር አድርገው ሲልኩልን፤ የምንቀበልዎ ከፍ ባለ ደስታ ብቻ ሳይሆን፤ እጅግ ከፍ ባለ አክብሮት ነው** ... " ብሏል። በዚያን ዘመን ኢትዮጵያ የአሜሪካ እርዳታ በጣም የሚያስፈልጋት ጊዜ ነበር። የኤርትራ ጉዳያችን የተጀመረውና የተፈጸመው፤ በትሩማን ጊዜ ነው። ጃንሆይ በሩዝቬልት ላይ የጠበቁትን ያህል ባይሆንም፤ በብዙ የኢትዮጵያ ጉዳዮች ላይ የአሜሪካ ድጋፍና እርዳታ አልተለየንም ... " " ... **ከእንግዲህ ወዲህ የኢትዮጵያን ነፃነት የሚደፍር እንደማይኖር እርግጠኛ**

መሆን አለበዎት ... " ሲል ፍራንክለን ዲ.ሩዝቬልት በስዌዝ ካናል ለኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት የተናገረው ቃል ትክክለኛ ግቡን የመታ መሆኑን ታሪክ ምንጊዜም ሲያወሳው ይገባል።

እ.ኤ.አ በሰኔ 1943 ዓ.ም፤ የይልማ ዴሬሣ ፍሬያማ ሚሲዮን በከፈተው በር፤ በሁለቱ አገሮች መካከል የተዘረጋው መልካም የዲፕሎማቲክ ግንኙነት፤ እንግሊዞች በኢትዮጵያ ነፃነት ላይ እያንዣበቡ ያሳዩት የነበረውን ዕብሪት ምን ያህል እንደአዳከመው የማየት ዕድል አጋጥሞናል። ለሁለተኛው የእንግሊዞች ውል፤ ሎርድ ደላዋር ለድርድሩ አዲስ አበባ ሲገባ ይዞት የመጣው የበላይነት ስሜትና ውሉን ፈርሞ ሲመለስ ይዞት የሔደው መንፈስ ልዩነቱ ምን ያህል የጐላ እንደሆነ በሚገባ አይተናል።

በዚያን ጊዜ አሜሪካኖች በኢትዮጵያ ላይ የሚደረገው የታላቋ ብሪታንያ ጫና ምን ያህል እንደነበረ አድፍጠው የሚከታተሉ በመሆናቸውና፤ በዘመናዊው ዕውቀት የበሰሉት መልዕክተኞቻችንም ለኢትዮጵያ የነፃነት መብት ጠንክረው በመሟገታቸው፤ ኧርል ደላዋር እንደአሰበውና እንደተመኘው አልተሳካለትም።

ውሉ በተፈረመ ሁለት ወር ባልሞላ ጊዜ ውስጥ ደግሞ፤ የአሜሪካው መሪ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን በስዌዝ ካናል ጋብዞ ማነጋገሩ፤ ኢትዮጵያ ብቻዋን እንዳልሆነችና ከእንግዲህ ወዲህ ነፃነቷም እንደማይደፈር፤ የበለጠ ለማስገንዘብ ችሏል።

**Ref:**

a/ አክሊሉ ሀብተወልድ የቀ.ኃ.ሥ
ጠቅላይ ሚኒስትርና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር

b/ National Archives 884001 Selassie,
Haile/2-1945 Feb. 19,1945

c/ National Archives 884 001 Selassie,
Haile/2-2745

# ምዕራፍ ፱

## የቸርችል ያልተጠበቀ ግብዣ

በያልታ የተደረገው የሦስቱ ታላላቅ መንግሥታት ስብሰባ (አሜሪካ፣ እንግሊዝና መስኮብ) ሲፈጸም፣ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት በስዌዝ ካናል ከኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ከቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ጋር ለመገናኘት ቀጠሮ ማድረጉን ለጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል ገለጸለት። በዚህ ጊዜ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ አንቶኒ ኤደን፣ ጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል የኢትዮጵያን ንጉሠ ነገሥት ካይሮ እንዲመጡ ጋብዞ ቢያነጋግራቸው የተገባ ይሆናል ሲል አሳሰበ። ሚስተር ቸርችልም ከሚኒስትሩ ጋር በመስማማት ለንጉሠ ነገሥቱ ጥሪው እንዲላክላቸው አዘዘ።

በአዲስ አበባ የታላቋ ብሪታንያ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ሚስተር ሮበርት ሐው፣ ከጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል የተላከው መልዕክት ዕሁድ የካቲት 11 ቀን 1945 ዓ.ም እንደደረሰው፣ ለንጉሠ ነገሥቱ ልዩ ጸሐፊ ለአቶ ተፈራወርቅ ኪዳነወልድ ደውሎ ጃንሆይን በአስቸኳይ እንደሚፈልጋቸውና የሚሰጠውም ቀጠሮ በማግሥቱ ሰኞ 12/02/45 ከእኩለ ቀን ከስድስት ሰዓት በፊት እንዲሆን ጠየቃቸው። አቶ ተፈራወርቅም ወዲያውኑ በሰጡት መልስ፣ ሚኒስትሩ እንደጠየቀው ሰኞ ከጠዋቱ አራት ሰዓት ንጉሠ ነገሥቱን ለማግኘት የሚቻል መሆኑን ነገሩት። ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሩም በተሰጠው ቀጠሮ ከጠዋቱ በ4 ሰዓት ገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ለመገኘት መስማማቱን አስታወቀ።

ሰኞ የካቲት 12 ቀን 1945 ዓ.ም ከንጋቱ በ12 ሰዓት ላይ የአንድ አውሮፕላን የመነሻ ድምፅ የእንግሊዙን ሚኒስትር ከእንቅልፉ ስለቀሰቀሰው፣ ከአልጋው ቸር ብሎ በመውረድ ይህ በዚህ ሰዓት የሚነሳ አውሮፕላን የማን እንደሆነ ለማወቅ የመረጃ ክፍሉን ጠየቀ። የዩናይትድ ስቴትስ ኦፍ አሜሪካ የኤርፎርስ ልዩ አውሮፕላን፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ከጥቂቶች ተከታዮቻቸው ጋር አሳፍሮ መነሳቱ ተነገረው። ወዲያው በኢትዮጵያ አካባቢ አገሮች ውስጥ ካሉት የእንግሊዝ አውሮፕላኖች አንዱን አግኝቶ ወደ ካይሮ ለመጓዝ ዝግጅት ጀመረ። እንደአጋጣሚ አንዲት ትንሽ አውሮፕላን ከኤደን አዲስ አበባ መጥታ ያረፈች አገኘ። ከመሣፈሩ በፊት፣ አቶ ተፈራወርቅን በስልክ አግኝቶ እንዴት የጃንሆይ መሔድ አልተነገረኝም። ሰኞ ሌሊት መሣፈራቸውን ባውቅ ኖሮ ትናንት እሁድ ከጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል የተላከላቸውን ጥሪ አቀርብላቸው ነበር ብሎ ከፍተኛ ቅሬታውን ገለጠ። የጃንሆይ ልዩ ጸሐፊ ለእሳቸው ምንም ነገር እንዳልተነገራቸውና ምንም ነገር አለማወቃቸውን አስረዱት። ጠቅላይ ሚኒስትሩ ቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው ዜናውን እንደሰሙ፣ ለእንግሊዙ ሚኒስትር ስልክ ደውለው፣ እኔ የምረዳው ነገር እንዳለ ንገረኝ ብለው ጠየቁት። ሚስተር ሐው፣ በታላቋ ብሪታንያ መንግሥት እንደራሴ ላይ የምትፈጽሙት ሁሉ እጅግ የሚያሳዝን ነው፡ ይህንንም ለመንግሥቴ አቀርባለሁ። ትናንት እሁድ ጃንሆይን አግኝቼ ከመንግሥቴ የተላከውን ትልቅ ጉዳይ ማቅረብ ስችል፣ ልዩ ጸሐፊው ጃንሆይ በአውሮፕላን ተሳፍረው ከሔዱ በኋላ፣ ሰኞ በ4 ሰዓት ቀጠሮ ሰጠኝ። ከዚህ የበለጠ በደል የለም።



ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከሩዝቬልት ቪዚት በኋላ፤ በካይሮ ከጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችልና ከውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ከአንቶኒ ኤደን ጋር፤

ለማናቸውም እኔ አሁኑኑ ወደ ካይሮ ስለምሄድ፤ ለእርስዎ የምናገረው የለኝም ብሏቸው ሄደ። እዚህ ላይ እንደሚታየው የእንግሊዙ ሚኒስትር የተናደደውና ቅሬታውን ያሰማው፤ የጃንሆይ መሄድ እየታወቀ እንዴት በሌሉበት ቀጠሮ ይሰጠኛል? በማለት ነው እንጂ፤ የጃንሆይ በሩዝቬልት መጠራት ለምን አልተነገረኝም ብሎ አይደለም። ቢትወደድ ጉዳዩ በጣም አሳሰባቸው። በእንግሊዝ ለጋሲዮን በኩል የደረሰውን ሁኔታ የሚገልጥ ልዩ ቴሌግራም ለጃንሆይ ላኩ። ከጃንሆይ ምንም ዓይነት መልስ ሳይላክላቸው ቀረ። የአሜሪካን ለጋሲዮን ጉዳይ ፈጻሚ ግን፤ የጃንሆይን ስዊዝ ካናል በደህና መድረስና ያላቸውንም ፕሮግራም በአቶ መኰንን ደስታ የፖስታ ቴ.ቴ ሚኒስትር አማካይነት በየሰዓቱ ለግርማዊት እቴጌ ያቀርብ ነበር።

የእንግሊዙ ሚኒስትር ሚስተር ሐው፤ ሰኞ የካቲት 12 ቀን 1945 ዓ.ም እኩለ ቀን ላይ ከአዲስ አበባ ተነስቶ በዚያች ከኤደን በመጣች ትንሽ አውሮፕላን በየ400 ኪ.ሜ በረሃ ላይ እያረፈ በውድቅት ሌሊት እንደምንም ካይሮ ደረሰ። በማግሥቱ ማክሰኞ (13/02/45) ሚስተር ሐው ከቸርችልና ከኤደን የተላከውን መልዕክት በስዊዝ ካናል ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር ለሚገኘው ለጓደኛውና ለአቻው ለአሜሪካ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ልክ፤ ለጃንሆይ በአስቸኳይ እንዲያቀርብለት ጠየቀው። ሚኒስትር ካልድዌል ንጉሠ ነገሥቱ ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጋር የሚያደርጉትን ንግግር ፈጽመው ከማረፊያቸው እንደተመለሱ፤ ሚስተር ሐው የላከውን ደብዳቤ አቀረበላቸው። ወዲያው ጃንሆይ ራስ ካሣ፣ አክሊሉ ሀብተወልድና ይልማ ዴሬሣ ባሉበት አጭር ስብሰባ አደረጉ።

ከቸርችል ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የተላከው መልዕክት የሚከተለው ነበር። " ... እርብ የካቲት 16 ቀን 1945 ዓ.ም ከቀትር በኋላ አንቶኒ ኤደንና እኔ ከአቴንስ ተነስተን ካይሮ እንደርሳለን። በዚያ በሚገኘው በታላቋ ብሪታንያ ኤምባሲ ከግርማዊነትዎ ጋር ተገናኝተን በጋራ ጉዳዮቻችን ላይ ሐሳብ ብንለዋወጥ ደስ ይለኛል ... "

ዊንስተን ቸርችል

ጃንሆይ የቸርችልን መልዕክት ካዳመጡ በኋላ፤ ወትሮ እንደሚያደርጉት የሰበሰቧቸውን ሰዎች ምን ታስባላችሁ? ብለው ሳይጠይቁ የራሳቸውን አስተያየት አስቀደሙ።

" ... እኔ የመጣሁት ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጥሪ ደርሶኝ የእሳቸው እንግዳ ሆኜ ነው። በዚህ ማህል ጣልቃ ገብቶ ከሚስተር ቸርችል የመጣልኝ ጥሪ፤ ተገቢም አስፈላጊም ሆኖ አላየውም። የታላቋ ብሪታንያ ጠቅላይ ሚኒስትር እኔን ለማነጋገር የሚፈልጉ ከሆነ፤ በሌላ ጊዜና በሌላ ቦታ እንድንገናኝ ጥሪውን አዲስ አበባ ሊልኩልኝ ይችላሉ። አሁን ግን በአንድ መልክ የመጣሁበትን ጉዳይ ጨርሼ ወደ አገሬ መመለስ እንጂ፤ ሌላ ጉዳይ ማቀላቀል አልፈልግም ... " አሉ።

ጃንሆይ በዚህ አስተያየታቸው ፀንተው የቸርችልን ጥሪ አልቀበልም ካሉ፤ የሚደርስብንን ችግር እንዴት አድርገን እንቋቋመዋለን? በማለት አቶ አክሊሉና አቶ ይልማ ሲጨነቁ፤ ራስ ካሣ ደርሰው ቀናውን መንገድ አስያዙላቸው። በጣም ጥሩ የሆነው፤ ራስ ካሣ ምክራቸውን እንዲሰጡ የጠየቋቸው ራሳቸው ጃንሆይ መሆናቸው ነው። ራስ ካሣም ጥያቄውን ተቀብለው የሚያስቡትንና የሚመስላቸውን ገልጠው ተናገሩ።

" ... ጃንሆይ! የዚህን ፖለቲካ የተባለውን የተለባበሰ ኑሮና የየመንግሥታቱን ጠባይ ከእርስዎ የበለጠ የሚያውቅ የለም። ከየመንግሥታቱ የሚያደርጉትም ግንኙነት የትኛው እንደሚጠቅመንና የትኛው እንደሚጎዳን ለጃንሆይ እንደሚታየው ለእኛ አይታየን ይሆናል። ቢሆንም በእኔ በኩል የሚታየኝን ከመናገር አላስቀረውም። ጃንሆይ የተናገሩት እውነትና ትክክለኛ ነገር መሆኑ በሚገባ ተሰምቶኛል። የአሜሪካው መሪ ጋበዞ፣ በወግ ተቀብሎ፣ አገራችንን ኢትዮጵያን ለመርዳት ልቡ በከጀለበት ሰዓት፣ የእንግሊዞች የደንቃራ ግብግቦ ይዞ ብቅ ማለት፣ የጨዋ አሠራርና የሚያስደስት አለመሆኑን ማንም አይስተውም። እኛን ቅር የሚለን፣ ጃንሆይ እንዳሉት ከቤታችን አምጥተው በጋበዙንና በአስተናገዱን፣ ከዚህም በላይ ችግራችንን ገልጠን ያወያየናቸው ወዳጆቻችን አሜሪካኖች እንዳይታዘቡን ነው። ይኸውም ትናንት እንግሊዞች ባደረሱባቸው በደል ተገን ሆነን እንድንረዳቸው ከተስማማን በኋላ፣ ዛሬ ደግሞ ከእኛ ቤት ወደ እነሱ ቤት የተጋበዙት ምን ለመነጋገር ነው? ብለው ሐሳብ እንዳይገባቸው ነው። ... እኔ እንደዚህ ስናገር፣ ነገሩ ሁሉ እኔ እንዳልኩት ብቻ ይሄዳል ማለት አይደለም። ሊሆንም ይችላል ብሎ ማሰብ ይገባል ለማለት ነው። በሌላ በኩል ደግሞ ልናስብበት የሚገባ ትልቅ ጉዳይ አለ። እንግሊዞችን ወደ ጠላትነት ከመግፋት፣ ወደ ወዳጅነት መሳብ እጅግ አስፈላጊ መሆኑን የሚክድ የለም። ጃንሆይ ከእንግሊዞች ጋር በትዕግሥት ያሳለፏቸው ጉዳዮች ብዙዎች ናቸው። ለዚህ ዛሬ ለጋበዝዎ የእንግሊዞች የሚኒስቴሮች አለቃ (ጠቅላይ ሚኒስትር) አሥር ጊዜ ጽፈውለት፣ መልስ የሚሰጥዎ ከአራትና ቢበዛ ከአምስት አይበልጥም ነበር። ዛሬ ግን፣ በሥላሴዎች ቸርነት ነገር ተለውጦ፣ እሱ ራሱ ከሌላ እሩቅ አገር ተነሥቶ፣ በአውሮፕላን ተጉዞ፣ እርስዎ አሉበት አካባቢ አገር ድረስ መጥቼ እርስዎን ማግኘትና ማነጋገር እፈልጋለሁ ሲል፣ እንዴት ተደርጎ አሻፈረኝ ይባላል? ... የአሜሪካኑ ግብዣ የመጣው ተፈልጎና ተደክሞበት ነው። የእንግሊዙ ጥሪ ግን የመጣው፣ ማንም ሳያስበው ማንም ሳይጠብቀው እዚሁ እተጋበዝንበት አሜሪካኖቹ ቤት ድረስ ነው። ስለዚህ፣ ለመልካሙና ለሰላሙ ግንኙነታችን ሲባል፣ የእንግሊዞቹን ጥሪ መቀበል የሚያስፈልገን መሆኑን፣ እነዚህ ልጆች አክሊሉና ይልማ አሜሪካኖቹን ቢያስረዷቸው የተሻለ ይሆናል። እንግሊዞችና አሜሪካኖች ከአንድ ዘር የመነጩ ወንድማማቾች ናቸው ስለሚባል፣ ችግራችንን በጥሞና ካስረዳናቸው ቅሬታ ሊሰማቸው አይችልም። ... እኔ እንግዲህ የታየኝንና የሚመስለኝን ተናግሬያለሁ። ጃንሆይ ይወስኑ! ... "

ጃንሆይ የራስ ካሣ ምክር ከልባቸው ገብቷል። በተጨማሪ መነጋገር አስፈላጊ ሆኖ አላገኙትም። " ... ራስ ካሣ እንዳለው፣ አክሊሉና ይልማ አሜሪካኖቹን አነጋግሩና የሚሏችሁን ሰምታችሁ ንገሩን ... " ብለው ትዕዛዝ ሰጡ። አቶ አክሊሉና አቶ ይልማ የፕሬዚዳንት ሩዝቬልትን ልዩ ረዳትና እንዲሁም በኢትዮጵያ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሩን ካልድዌልን አነጋገሩ። በአሜሪካኖቹ አስተያየት፣ የጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችልን ጥሪ ንጉሠ ነገሥቱ ሊቀበሉት የሚገባ ነው። ቀጠሮው የሚመጣው ዓርብ (16/02/45) ቢሆንም፣ እስከዚያው ድረስ ላሉት ሦስት ቀናቶች፣ ንጉሠ ነገሥቱ እኛ እዚሁ አዘጋጀንላቸው ማረፊያቸው ሊቆዩ ይችላሉ። ካይሮ ሄደው ቸርችልን ካነጋገሩ በኋላ ማታውኑ እዚሁ ተመልሰው፣ በማግሥቱ ቅዳሜ ጠዋት ባመጣናቸው አውሮፕላን አዲስ አበባ እንመልሳቸዋለን። ... የሚል መልስ ሲያገኙ፣ አቶ አክሊሉና አቶ ይልማ ወደ ጃንሆይ ተመልሰው መልካሙን ዜና አስረዱ። ጃንሆይና ራስ ካሣ በጣም ተደሰቱ። ሆኖም ጃንሆይ አንድ ቅር የሚለኝ ነገር አለ አሉ። " ... እኔ እስከ ካይሮ ድረስ ከምጓዝ፣ ለምን ጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል እዚሁ አለሁበት ማረፊያዬ ድረስ መጥተው

እንነጋገርም? ... " የሚል ጥያቄ አቀረቡ። አቶ አክሊሉ፤ " ... ቸርችልና ኤደን እርስዎን ለማየት የሚመጡት ከአቴንስ ነው። ካይሮ ካረፉ በኋላ፤ እንደገና ወደ እዚህ ስዌዝ ካናል ድረስ እንዲመጡ መጠየቅ የተገባ አይመስለኝም ... " አሉ። ጃንሆይ፤ ምንአለበት! ይሞከርና ይታይ! አሉ። አቶ ይልማ ቀጠል አደረጉና፤ " ... ይህን ሐሳብ አቅርበን እንቀበልም ከተባልን ምን ማድረግ እንችላለን? ... " ሲሉ ጠየቁ። ጃንሆይ ይሞከር! ግዴለም! የሚል የተቀረጠ ትዕዛዝ ሰጡ። ለቸርችል ቴሌግራሙ ተላለፈ። ጠቅላይ ሚኒስትሩ ጊዜ ሳይወስድ ወዲያውኑ መልሱን ሰጠ። " ... እኔ ስዌዝ ካናል ድረስ መምጣት አልችልም ... " አለ። አቶ አክሊሉና አቶ ይልማ የተናገሩት ደረሰ። የጃንሆይ ወደ ካይሮ መሄድ የግዴታ አስፈላጊ ሆነ። ጃንሆይ ሌላ ጥያቄ ጨመሩ። ከዚህ ካለሁበት "Payne Field" እስከ ካይሮ ደርሶ መልስ ትራንስፖርቱን የሚያዘጋጁት እንግሊዞች ከሆኑ ደስ አይለኝም አሉ። አቶ አክሊሉ የአሜሪካኑን ሚኒስትር ሚስተር ካልድዌልን ጠየቁት። " ... እኛ ካይሮ ወስደን እንመልሳቸዋለን። ጃንሆይ ወደ አገራቸው እስከሚመለሱበት ቀን ድረስ፤ የፕሬዚዳንት ሩዝቬልት የክብር እንግዳ ስለሆኑ፤ ትራንስፖርቱንም ሆነ ፀጥታውን የምናዘጋጅ እኛ ስለሆንን አታስቡ ... " አላቸው። ጃንሆይ የፈለጉት ሆነላቸው። ራስ ካሣም እነዚህን ልጆች ይልማንና አክሊሉን "እግዚአብሔር ይባርካቸው" ብለው መረቋቸው። እዚህ ላይ ለውጤቱ የነ አክሊሉ ድካም ብቻ ሳይሆን፤ የራስ ካሣም የጠለቀ ምክር ምን ያህል እንደረዳ ያሳያል።

## የካይሮ ውይይት
## ከዊንስተን ቸርችል ጋር

እ.ኤ.አ ዓርብ የካቲት 16 ቀን 1945 ዓ.ም ወደ ማታ በ11 ሰዓት፤ ካይሮ በሚገኘው የታላቋ ብሪታንያ ኤምባሲ፤ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና የእንግሊዝ ጠቅላይ ሚኒስትር ዊንስተን ቸርችል ተገናኝተው ለአንድ ሰዓት ያህል ተነጋገሩ። ባለፉት አምስት ዓመታት በሁለቱ አገሮች በኢትዮጵያና በታላቋ ብሪታንያ መካከል የተፈጠረው ግንኙነት እጅግ ከፍ ያለና ብዙዎች ጉዳዮችን የያዘ ሲሆን፤ የጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችልና የንጉሠ ነገሥቱ ውይይት እንዴት በአንድ ሰዓት ጊዜ ብቻ ሊወሰን ቻለ? የሚል አስተያየት ከፖለቲካ ታዛቢዎች ተሰጥቶበት ነበር።

በኢትዮጵያ በኩል ንጉሠ ነገሥቱና ቸርችል ተገናኝተው ይነጋገራሉ ተብሎ ያልታሰበና ያልተጠበቀ ስለነበረ፤ ዝግጅት አልተደረገም። በታላቋ ብሪታንያ ባለሥልጣኖችም በኩል፤ ንጉሠ ነገሥቱን የአሜሪካ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጋብዞ ስዌዝ ካናል ድረስ በማስመጣት ስለአነጋገራቸው፤ እኛም በኢትዮጵያ ጉዳይ ውስጥ በብዙ ረገድ ተካፋዮች በመሆናችን፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ማግኘት ለምን ይቀርብናል? በሚል መንፈስ እንጂ፤ በዚያን ሰዓት በሁለቱ አገሮች መካከል ንግግር መደረግ ያለባቸው አጣዳፊ ጉዳዮች አልነበሩም።

በቀጠሮው ሰዓት ዊንስተን ቸርችል ንጉሠ ነገሥቱን በኤምባሲው ሲቀበላቸው፤ " ... ከሁሉ በፊት እርስዎ እንደጠየቁኝ ስዌዝ ካናል ማረፊያም ድረስ መምጣት ያልቻልኩት፤ ረዘም ላለ ሰዓት በተሽከርካሪ ጉዞ ማድረግ የጤና ችግር ስለሚፈጥርብኝ በመሆኑ ይቅርታ ያድርጉልኝ ... " አላቸው። ከዚህም አያይዞ፤



የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት እ.ኤ.አ በሚያዝያ 1945 ዓ.ም ሳንፍራንሲስኮ ላይ ሲቋቋም ቻርቱን የፈረሙት የኢትዮጵያ ዋና መልዕክተኛ አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ ናቸው። በስተጀርባ ከግራ ወደ ቀኝ የቆሙት፤ አቶ ምናሴ ለማ፣ አቶ አማኑኤል አብርሃም፣ ብላታ ኤፍሬም ተወልደ መድህን እና ዶክተር አምባዬ ወልደማርያም ናቸው።

"… አገሬ ኢትዮጵያ፤ ባለፈው ታሪኳ በሊግ ኦፍ ኔሽን ፍርድ ተነፍጓት ብዙ መከራ የደረሰባት ብትሆንም፤ አዲሱ የተባበሩት መንግሥታት ለአገሮች ነፃነትና መብት፤ ለሕዝቦች እኩልነትና ደህንነት ተግባሩን በትክክል ይፈጽማል ብላ፤ ሙሉ ተስፋ ታደርጋለች … "

(አክሊሉ ሀ.ወ ሚያዝያ 1945 ዓ.ም)

ከግርማዊነታቸው ጋር ለመጀመሪያ ጊዜ የተዋወቀው፤ በ1924 ዓ.ም በአልጋወራሽነታቸው ዘመን እንግሊዝን በጎበኙበት ጊዜ በባኪንግሐም ቤተመንግሥት በተደረገላቸው ግብዣ ላይ መሆኑን አስታወሳቸው። ጃንሆይም በሰጡት መልስ፤ " ... ንጉሥ ጆርጅ ፭ኛ ለእኔ ክብር ባደረጉት ግብዣ ላይ፤ ከርስዎ ጋር መተዋወቄን እኔም አስታውሳለሁ። ባልሳሳት፤ እርስዎ በዚያን ጊዜ የካቢኔ ሚኒስትር አልነበሩም? ብለው ጠየቁት። ቸርችል ተገረመ። ያስዎት የማስታወስ ኃይል የሚያስደንቅ ነው። ጃንሆይ እንደአስታወሱት እኔ በዚያን ጊዜ የባልድዊን መንግሥት የገንዘብ ሚኒስትር (Chancellor Of Exchequer) ነበርኩ ካላቸው በኋላ፤ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሬ አንቶኒ ኤደን እኔን ጃንሆይ በጣም ያውቁኛል እያለ ሲፎክር ሰምቸዋለሁ። እሱንስ ያስታውሱታል? ብሎ ጠየቃቸው። ሚስተር ኤደንን ጃንሆይ ደህና አድርገው እንደሚያውቁት አስረዱ። " ... ኢትዮጵያ ፋሽስት ባደረሰባት ጥቃት የገፔሹን የመንግሥታት ማህበር ፍርድ ለማግኘት በምንሟገትበት ጊዜ፤ ሚስተር ኤደን የእኛ ዋና ረዳት ነበሩ። እኛም ራሳችን ለአቤቱታ ጀኔቭ በሄድንበት ጊዜ አግኝተናቸዋል። ከዚያም በስደት እንግሊዝ አገር እንደደረስን፤ ሚስተር ኤደን በውጭ ጉዳይ ሚኒስትርነታቸው ከአንድም ሁለት ጊዜ ከማረፊያችን ድረስ መጥተው ጠይቀውናል። ሌላ የረሳሁት ነገር ካለ፤ እሳቸው ይጨምሩበት ... " ብለው ንግግራቸውን አቆሙ። ቸርችል በጣም ሳቀ። " ... ጃንሆይ ከተናገሯቸው ውስጥ ምን ምን እንደሚያስታውስ እሱን ይጠይቁት እንጂ፤ እርስዎ የረሱት ነገር ኖሮ እሱ የሚጨምርበት እንደሌለ፤ እኔ አረጋግጥልዎታለሁ ... " አለ። እዚህ ላይ ጃንሆይም ሳቁ። ...

**ቸርችል**

አሁን ወደ ዋናው ጉዳያችን እንመለስና፤ ዛሬ ግርማዊነትዎን የምቀበለው በታላቅ ደስታ ነው። በፋሽስቶች ጭካኔ ብዙ መከራ የተቀበለችው አገርዎ ኢትዮጵያ፤ ነፃነቷን ለማስመለስና እርስዎም ከአባቶችዎ የወረሱት የንጉሠ ነገሥት ዙፋንዎ እቦታው በመመለሱ፤ ከዚህ ቀደም የተሰማኝን ደስታ በልዩ ልዩ መልዕክት ብገልጥልዎትም፤ ዛሬም እርስዎን በአካል በማግኘቴ ብደግመው የተገባ ይመስለኛል። ታላቋ ብሪታንያም፤ በዚያ በአስቸጋሪ ዘመን የኢትዮጵያን ነፃነት ከክፉዎቹ ፋሽስቶች እጅ ለማላቀቅ፤ በፈጸመችው መሥዋዕትነትን በጠየቀ ተግባር ኩራት ይሰማታል። የነፃነት ጉዞ ወደ ኢትዮጵያ በተደረገበትም ጊዜ፤ ጀግኖቹ አርበኞችዎ ከታላቋ ብሪታንያ ጦር ኃይል ጋር ተሰልፈው ያደረጉትን ተጋድሎ በአድናቆት እናስታውሳቸዋለን። የምንኖርበትን ዓለም ለማጥፋት የተነሱት ናዚስቶችና ፋሽስቶች፤ በአሁኑ ሰዓት እየተደመሰሱ የሰው ልጅ ነፃነትና መብት ቢመለስም፤ ክፉዎቹ ያደረሱትን ጥፋት እንደገና ለማቋቋም ያለው ችግር በቀላሉ የሚወገድ አይደለም። በኢትዮጵያም ፋሽስት ያፈረሰውን ሁሉ ለመጠገን ግርማዊነትዎ ላይ የወደቀው ከባድ ሥራ ምን ያህል እንደሆነ እንገምታለን። ሆኖም ነፃነት ካለ፤ ማንኛውም ችግር ጊዜ ከመውሰዱ በቀር እንደሚወገድ የታወቀ ስለሆነ፤ ግርማዊነትዎ ባለው የጠነከረ መንፈስ ፈተናውን እንደሚወጡት እርግጠኛ ነኝ። በአገሬ በታላቋ ብሪታንያና በግርማዊነትዎ መንግሥት መካከል ያለው መልካም ግንኙነት፤ በደህና ሁኔታ የቀጠለ መሆኑንና አሁን በቅርቡም የተደረገው ሁለተኛው ስምምነት፤ በመልካም መግባባት እንደተከናወነ ሰምቻለሁ። አሁን በግርማዊነትዎ በኩል የሚገለጽልኝን አስተያየትና ሐሳብ ለማዳመጥ ተዘጋጅቻለሁ።

## የጃንሆይ መልስ

ስለ አገሬና ስለ እኔም፤ ክቡርነትዎ በተናገሩት ሁሉ ከልብ አመሰግናለሁ። ከሁሉም በፊት ኢትዮጵያ በፋሽስት የተገፈፈውን ነፃነቷን ለማስመለስ፤ በክቡርነትዎ የሚመራው የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ያደረገላትን ውለታ መቸውንም እንደማትዘነጋው ለክቡርነትዎ ማረጋገጥ እወዳለሁ። ከክቡርነትዎ ጋር ተገናኝቶ ለመነጋገር የሚቻል መሆኑን ከአዲስ አበባ ከመነሣቴ በፊት አውቄው ቢሆን ኖሮ፤ በአገሮቻችን መካከል ስላሉት ግንኙነቶች ጉዳዩ በቀጥታ የሚመለከታቸውን ሚኒስትሮቼን ይዤ በመምጣት በዝርዝር ለማስረዳት ይቻል ነበር። ነገር ግን የክቡርነትዎ ጥሪ የደረሰኝ፤ በፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ተጋብዤ ስዌዝ ካናል የመጣሁበትን ጉዳይ ከፈጸምኩ በኋላ፤ ወደ አዲስ አበባ ለመመለስ አንድ ሌሊት ሲቀረኝ ነው። ሆኖም መገናኘታችንና በአንዳንድ ዋና ዋና ጉዳዮች ላይ ሐሳብ ለመለዋወጥ መቻላችን የሚያስደስት ነው።

ክቡርነትዎ እንደጠቀሱት፤ የተከበሩ መላክተኛዎ ሎርድ ደላዋርና እኔ የመረጥኳቸው መልዕክተኞች በአገሮቻችን ግንኙነት ጉዳይ በሰፊው ተነጋግረው የተስማሙበትና የተፈረመው ሁለተኛው ውል፤ ከመጀመሪያው በተሻለ የኢትዮጵያን አስተዳደር መብት የሚጠብቅ በመሆኑ፤ በመልካም መንፈስ ተቀብለነዋል። ሆኖም አንድ የማነሳው ነጥብ አለ። ይኸውም፤ ኦጋዴንና ሪዘርቭድ ኤሪያ የተባለው ግዛታችን፤ በአዲሱም ውል ቀድሞ እንደነበረው የታላቋ ብሪታንያ የጦር ኃይል ማስፈሪያ ሆኖ እንዲቆይ መደረጉን ነው። በእኛ ጥናትና ግምት፤ በአሁኑ ሰዓት ላልተፈጸመው የዓለም ጦርነት፤ ኦጋዴንና ሪዘርቭድ ኤሪያ የተባለው ግዛታችን የሚሰጠው ጥቅም አልታየንም። ይሁን እንጂ፤ በዚህ በአዲሱ ሁለተኛው ውል እንደአለፈው ጊዜ እንዲሆን፤ በክቡርነትዎ የሚመራው የጦር ካቢኔ አጥብቆ ጠይቋል ተብሎ ስለተነገረኝ፤ የክቡርነትዎን ፍላጐት ተቀብዬ እንዲፈጸም አድርጌያለሁ። አሁን ይህንን ጉዳይ ያነሳሁት፤ የተፈረመው ውል እንደገና እንዲታይ ወይም እንዲሻሻል ለመጠየቅ አይደለም። እኔ የማሳስበው፤ <u>ኢትዮጵያ ኦጋዴንና ሪዘርቭድ ኤሪያ የተባለውን ግዛቷን ለታላቋ ብሪታንያ ጊዜያዊ ጦር ማስፈሪያ እንዲሆን ያደረገችውን ከግምት ውስጥ በማስገባት፤ ለሁለተኛው የዓለም ጦርነት የበኩሏን እርዳታ እንዳበረከተች እንዲቆጠርላት ነው።</u> ሎርድ ደላዋር የክቡርነትዎ ዋና መላክተኛ ሆነው እኛ ዘንድ እንደመጡ፤ ይህ ኦጋዴንና ሪዘርቭድ ኤሪያ የተባለው ግዛት ለታላቋ ብሪታንያ ጦር ማስፈሪያ እንዲሆን ሲደረግ፤ በኪራይ ስም ገንዘብ ለመክፈል የክቡርነትዎ መንግሥት ማሰቡን ገልጸውልን ነበር። እኛ ግን በዓለም ጦርነት ምክንያት ታላቋ ብሪታንያ የሚያስፈልጋትን ለመርዳት ገንዘብ አንቀበልም ብለን መልሰናቸዋል። ስለዚህ፤ ለሁለተኛው የዓለም ጦርነት ኢትዮጵያ በአቅሟ የሚቻላትን እንደፈጸመች ቢቆጠርላት በጣም ደስ ስለሚለን፤ የክቡርነትዎ አስተያየት እንዲያርፍበት እናሳስባለን። ከዚህ ቀጥሎ ሌሎች ለክቡርነትዎ የምጠቅሳቸው ሦስት ጉዳዮች አሉኝ። እነዚህም፤

1ኛ/ የኤርትራን ወደ እናት አገሯ ወደ ኢትዮጵያ መመለስ እጅግ የምናስብበት ጉዳይ ስለሆነ፤ ከዚህ ቀደም በተገለጸልን መልካም አስተያየት መሠረት፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት እርዳታውን እንደሚቀጥልልን ተስፋ እናደርጋለን።

2ኛ/ የዚህ የሁለተኛው የዓለም ጦርነት የሰጠውን ትምህርት በመመርኮዝ፤ ለዓለም ሰላም ቋሚ ዋስትና የሚሰጥ የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ለማቋቋም በሚደረገው ዝግጅት፤ በሊግ ኦፍ ኔሽን የፍርድ በደል የደረሰባት ኢትዮጵያ፤ ረቂቁን የሚያዘጋጀው የሕግ ኮሚቴ አባል ሆና እንድታገለግል አመልክተናል። ለዚህም የክቡርነትዎ መንግሥት እንዲረዳን እናሳስባለን።

3ኛ/ ከጦርነቱ ፍጻሜ በኋላ በሚደረገው የዓለም የሰላም ጉባኤ ላይ፤ የኢትዮጵያ ተካፋይነት ምን ያህል ተገቢና አስፈላጊ መሆኑን የክቡርነትዎ መንግሥት እንደሚቀበለው አንጠራጠርም። በዚህ በሁለተኛው የዓለም ጦርነት በደረሰው ዕልቂት፤ ኢትዮጵያ የመጀመሪያዋ ተጠቂና የመጀመሪያዋ ነፃ ወጭ አገር በመሆኗ፤ ከሰላሙ ጉባኤ ሸንጐ መለየት እንደሌለባት፤ ሌሎቹም ታላላቅ አገሮች ትክክለኛ ውሳኔ ይሰጣሉ ብለን በተስፋ እንጠብቃለን። ክቡርነትዎ ጊዜ ወስደው በኢትዮጵያ በኩል ያለውን አንዳንድ ጉዳይ ለማዳመጥ ፈቃድዎ በመሆኑ አመሰግንዎታለሁ ... "

ዊንስተን ቸርችል ከጃንሆይ የቀረበውን ሐሳብ ካዳመጠ በኋላ፤ " ... እንግዲህ ! በሚቀጥሉት ወራት ውስጥ በአገሬ በሚደረገው የፖለቲካ ምርጫ፤ የታላቋ ብሪታንያ ሕዝብ የእኔን መሪነት ተስማምቶት ዕምነቱን የሚጥልብኝ ከሆነ፤ ለግርማዊነትዎ መንግሥት የሚያስፈልገውን እርዳታ ሁሉ ከመፈጸም ወደ ኋላ አልልም። ኢትዮጵያ ነፃነቷን አግኝታ እርስዎም የንጉሠ ነገሥትነት ዘውድዎ ተመልሶ ለማየት በመቻላችን ደስ ብሎኛል ... " በሚል ቃል ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ተሰናበታቸው።

ቸርችል ጃንሆይን ተቀብሎ ከአነጋገረ ከጥቂት ወራት በኋላ፤ በተደረገው የፖለቲካ ምርጫ የእንግሊዝ ሕዝብ በዚያ በክፉ የጦርነት ዘመን በቆራጥነት የፈጸመውን ሳያስብለት ቀርቶ ምርጫውን ስለነፈገው፤ የተቃዋሚው የሌበሩ ፓርቲ ድል አግኝቶ የክሊመንት አትሊ መንግሥት ተቋቋመ። የቸርችል መንግሥት ከወደቀ በኋላ አዲስ የመጣው የሌበር መንግሥት በኢትዮጵያ ላይ ምንም ዓይነት ችግር አልፈጠረባትም። ይልቁንም በኤርትራ ጉዳይ በቂ እርዳታ እንደሰገሠ ይታወሳል።

<u>መረጃ፡</u> ከዚህ በላይ በስድስተኛው ክፍል ውስጥ፤ በሰባተኛው፣ በስምንተኛውና በዘጠነኛው ምዕራፎች ላይ እንደቀረበው፤ ንጉሠ ነገሥቱ ከሩዝቬልትና ከቸርችል ጋር በስዌዝ ካናል ለመገናኘት እንዴት እንደቻሉና የንግግሩም ውጤት ምን መሆኑን የመጽሐፉ ደራሲ በአሜሪካንና በእንግሊዝ አገሮች ካደረገው ምርምር ሌላ፤ ዋና ዋና የሆኑትን ጉዳዮች በደበልጥ መተንተን የቻለው፤ <u>የቀ.ኃ.ሥ ጠቅላይ ሚኒስትር ጸሐፊ ትዕዛዝ አክሊሉ ሀብተወልድ በሰጡት መረጃ መሆኑን ለአንባቢዎቹ ይገልጻል።</u>

## ሙሶሊኒና ላቫል ፍርዳቸውን ተቀበሉ።



እ.ኤ.አ በሚያዝያ 1945 ዓ.ም ሙሶሊኒ በተቃዋሚዎቹ ተገድሎ በሚላኖ ከተማ አደባባይ ሬሣው ተዘርሮ ለሕዝብ እንዲታይ ተደረገ፤



ፒየር ላቫል ከሙሶሊኒና ከሂትለር ጋር ሆኖ የአገሩን ነፃነትና ክብር የበደለ ከሐዲ በመባል ተፈርዶበት በጥቅምት 1945 ዓ.ም በጥይት ተደብድቦ ተገደለ፤

## ፋሽስቱ ሙሶሊኒ

" ... ጦር ለወንዶች፣ መውለድ ለሴቶች ... " እያለ ይፎክር የነበረው ሰው፣ ሳይታኮስ ወይም ሳይዋጋ በፍርሃት ለጠላቶቹ እጁን ሰጥቶ ከተገደለ በኋላ፣ <u>ሬሣው በገመድ ተጐትቶ እንደታረደ ከብት በሉካንዳ ሜንጦ ላይ ተንጠልጥሎ ለሕዝብ እንዲታይ ተደረገ።</u> በክርስቲያን አገር በሰው ልጅ ላይ ይህን የመሰለ ሁኔታ ይፈጸማል ተብሎ የሚታሰብ አልነበረም።

እብደትና ብልህነት በተቀላቀለበት [illegible]ዩ፣ የልቡን እየሸኘ ላይ ላዩን በሚያሳየው የደፋርና የቆራጥ መንፈስ፣ በዓለም ላይ ኃይለኛና ወሳኝ መሪ ነው እየተባለ ይነገርለት ነበር። ኋላ ግን ሥልጣኑ ተደምስሶ፣ በጠላቶቹ ታድኖ ሲያዝና ለመገደል ሲቀርብ፣ [illegible]ልጽ የታየበት ያ ሁሉ ፍርሃትና መርበትበት በሰፊው ሲነገርለት የቆየው [illegible]ትና ጀግንነት የት ደረሰ? የሚል ጥያቄ ቀርቦ ነበር። ከዱቼ ይልቅ፣ በሞት አብራው መከተልን የመረጠችው እቁባቱ ወይዘሪት ክላራ ፔታቺ (Clara Petacci) ያደረገችው ውሳኔና ያሳየችው ቆራጥነት፣ እንኳንስ ተመልካቹን ሕዝብ ገዳዮቿንም በጣም አስገርሟ ነበር።

ቤኒቶ ሙሶሊኒ ታሪኩ እንደአሳየን፣ አባቱ የተናገረለት ትንቢትና እሱም ራሱ ያደረበት ምኞት ስለተገጣጠመ፣ ለሀያ ዓመታት የጣልያን ሕዝብ አስጨናቂ መሪ ብቻ ሳይሆን፣ ከጓደኛው ከሂትለር ጋር ገጥሞ ዓለምን በመበጥበጥ በታሪክ ውስጥ መግባቱን መካድ አይቻልም።

## ፈረንሣዩ ከሀዲ ፒየር ላቫል

ታሪክ እንደሚያሳየን እንደ አጋጣሚ ሁለቱ ወዳጆች ሙሶሊኒና ላቫል በአንድ ዘመን እ.ኤ.አ በ1883 ዓ.ም ተወልደው፣ በአንድ ዘመን በ1945 ዓ.ም በፈጸሙት ወንጀል ተገደሉ። ሌላው ደግሞ ተመሣሣይ የሆነው ታሪካቸው ላቫል እንደ ሙሶሊኒ የፖለቲካ ሕይወቱን ሲጀምር ሶሲያሊስት እንደነበረና ከዚያም ከጥቅም ጋር እየተሣሠረ ወደ ቀኞቹ ፓርቲዎች በመለወጥ የፋሽስቶችና የናዚስቶች ወገን ሆኖ መገኘቱ ነው። እኛ ኢትዮጵያውያን ላቫልን የምነጠላው ሙሶሊኒ ነፃነታችንን ገፍፎ ቅኝ ግዛቱ እንዲያደርገን በፈጸመብን ግፍ ነው። ፈረንሣዮች ደግሞ በላቫል ላይ ያሣደሩት ቂምና የሰጡት ፍርድ፣ ከሂትለር ጋር በቀጥታ ተሰልፎ የፈረንሣይን ነፃነት ለሂትለር በማስረከብ በፈጸመው ከባድ ወንጀል ነው። ከዚህም በላይ በብዙ ሺህ የሚቆጠሩ አርበኞችንና አይሁዳውያኖችን ከፈረንሣይ ውስጥ እያስለቀመ ለናዚስቶች ያስረከበና ያስጨረሰ ጨካኝ ከሀዲ በመሆኑ ነው።